# የኢትዮጵያ ሕገ መንግሥት ጉባኤ

## ቃለጉባኤ

## ጥራዝ

## 2

ጥቅምት 30 ኅዳር 7 /1987 ዓ.ም

አዲስ አበባ

## ማውጫ

## ጥራዝ 2

ጥቅምት 30 ቀን 1987 ዓ.ም ከጧቱ 3.00 ሰዓት በሕገ መንግሥት ጉባኤ አዳራሽ የተካሄደው የሕገ መንግሥት ጉባኤ የተመራው በጉባኤው ሊቀመንበር በዶ/ር ነጋሶ ጊዳዳ ሲሆን በቅድሚያ የጉባኤው ፀሐፊ አቶ አዲሱ ለገሠ በዕለቱ 526 የጉባኤው አባላት እንደተገኙ ገልጸው ጉባኤው ውይይቱን መጀመር እንደሚችል አሳስበዋል ::

ከዚያም የጉባኤው ሊቀመንበር ዶ/ር ነጋሶ ጊዳዳ የዕለቱ አጀንዳ በረቂቅ ሕገ መንግሥቱ አንቀጽ 3 ላይ እንደሚቀጥል አስታውቀዋል ::

በዚህም መሠረት አቶ ኤሊያስ ተሮ ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል ዛሬ አንድ ላይ ተዋቅረው የሚታዩት ሦስት የኢትዮጵያ ባንዲራ ቀለማት ለየብቻ ይሰቀሉ እንደነበር ፣ አፄ ሚኒሊክ ሦስቱን ቀለማት እንደ አንድ ባንዲራ ካዋቀሩ በኋላ ወደ ደቡብ የሀገሪቱ ክፍል በመዝመት ባንዲራውን ተቀበል በሚል የሲዳማን ፣ የጌዲኦን ፣ የወላይታን ሕዝብ መጨፈጨፋቸውን ታሪክ እንደሚመሰክር ፣ በዚህ ምክንያትም ባንዲራው በታየ ቁጥር ተጨፍጫፊዎች ተበዳይነታቸውን ጨፊጫፊዎች ደግሞ ራሳቸውን እንደ ነፃ አውጪ እንደሚያዩ ገልጸው ብሔር / ብሔረሰቦች ነፃነታቸውን ከተቀዳጁ ወዲህ ባንዲራውን በበዝባዦችና ጨፍጫፊዎች መቃብር ላይ ለማቃጠል የሚፈልጉ የሲዳማ ሕዝብ በርካታ እንደሆኑ አስረድተዋል ::

አያይዘውም አረንጓዴ ፣ ብጫ ፣ ቀይ የኢትዮጵያ ባንዲራ ሕዝቧ በባዕድ ኃይል ሳለመገዛትና የባዕድ ሀገር ባንዲራ በአገሩ እንዳይውለበለብ ከቀኝ ገዢዎች ታግሎ ነፃ የወጣበት በዚህም በዓለም አቀፍ ደረጃ የታወቀበት በመሆኑ አሁን ባንዲራውን መቀየር ለዓለም ለማሳወቅ በሚደረገው ጥረት የሰው ኃይልና ወጪ የሚጠይቅ እንደሆነ ጠቅሰው የብሔር / ብሔረሰቦችንና ሃይማኖቶችን እኩልነት የሚያንጸባርቅ ብሔራዊ አርማ በባንዲራው ላይ ተቀምጦ እና በዚሁ ትርጉሙ ተቀይሮ የሀገሪቱን ብሔራዊ ባንዲራነቱን እንዲቀል ማድረጉ እንደሚሻል ፣ አርማው ግን ለባለሙያ ብቻ ተትቶ በተወሰነ ጊዜ ውስጥ ተቀርጾ ለጉባኤው ቀርቦ ሊፀድቅ እንደሚገባው አመልክተዋል ::

በሌላም በኩል ወ/ሮ የአባይነሽ ካሳ ከክልል 3 አረንጓዴ ፣ ብጫ ፣ ቀይ የኢትዮጵያ ባንዲራ በኃይለሥላሴ ዘመነ መንግሥት በተለይ አርሶ አደሩ በፈረሰኛ ፣ በጭቃ ሹም ፣ በጉልተኛ ምርቱን የተነጠቀበት ፣ በደርግ ኢሠፓ ዘመንም ለባንዲራ ዝመት እየተባለ ወንድማማቾች የተራረዱበት ፣ አርሶ አደሩ ለሠፈራ ፕሮግራም

ሲባል ከቀየው የተነቀለበት በመሆኑ ሠርቶ አደሩም ሊያየው ስለማይሻ መደቡ ነጭ የሆነ የሠርቶ አደሩን ፍቅርና አንድነት እንዲሁም ከብዝበዛ ነፃ ለመውጣት ያደረገውን ትግል የሚያንፀባርቅ አርማ ባለው አዲስ ባንዲራ ሊቀየር እንደሚገባ ገልጸዋል ::

ቀጥለውም ሐጂ አህመድ ሐጂ መንዛሮ ከክልል 4 የኢትዮጵያ ባንዲራ የሕዝቦቿን አንድነት ፣ ነፃነትና አብሮ መኖር መሆን ሲገባው ከእግዚዘብሔር የተላከልህ ነውና ተቀበል በሚል በግዴታ በሚነሳ ጦርነት ደም የፈሰሰበት ምላስ ፣ እጅና እግር የተቆረጠበት ፣ ገገር መደቦች ራሳቸውን ያስከበሩበት ፣ የሌሎችን መብት ያፈኑበት የአፈናና የባርነት መሣሪያ እንደሆነ ፣ ይህ ባይሆን ኖሮ የኢትዮጵያ ሕዝቦች በጥላቻ ስሜት ያዩት እንዳልነበረ ፣ ዕውነቱ ይህ ሆኖ ሳለ ባንዲራውን እንደ ልዩ ነገር የሚቆጥሩትና የሚናገሩለት ቡድኖች በባንዲራው ስም የተጨቆኑት ሕዝቦች ታሪክ አያውቀውም ወይም መነሻው ተሳስቶ በባንዲራው ስም ምንም በደል አልደረሰም በሚል ቢኩራሩም አሁን የሰፈነው የብሔር / ብሔረሰቦችን እኩልነት ወደ ኋላ መመለስ እንደማይቻል ፣ ይልቁንም ክርክሩ ከትዝብት ላይ እንደሚጥላቸው አመልክተዋል ::

አያይዘውም በሚኒሊክ ዘመነ መንግሥት በአርሲ ብዙ ሕዝብ እንደተጨፈጨፈ እና መጠሪያውም "የወጣቶች ኩሬ" እንደምትባል ፣ ይህም ለዚህ ምስክር አንደሆነ ፣ በኃይለ ሥላሴ ዘመነ መንግሥትም ሠርቶ አደሩ ለጌታው አገልጋይ እንደነበረ ፣ ይህንንም በመቃወም ብዙ የሕይወት ጥፋት እንደደረሰ ፣ ደርግ ደግሞ የመሬት ግብርን ከመጨመሩም በላይ የአንድ ቤተሰብ በተለያየ ወቅት ድርጅቶችን በማቋቋም መዋጮ ያስከፍል እንደነበር ፣ ይህም አንሶት የሠርቶ አደሩን ትግል ለማዳከም በባንዲራ ስም ዝመት በሚል ደም ሲያፋስስ እንደነበረ አስረድተዋል ::

አክለውም የኢትዮጵያ ባንዲራ በባንዲራነቱ ራሱ በጭቁን ሕዝቦች ያደረሰባቸው በደል ባለመኖሩ እንዲሁም በዳዮች የሠሩት ሥራ አያመስክረባቸው በመሆኑ ዕውነተኛ ባንዲራ እንዲሆን የሁሉም ብሔር / ብሔረሰብና ሃይማኖቶች ዕኩልነት የሚያንጸባርቅ አርማ ተደርጎበት በኢትዮጵያ ባንዲራነቱ እንዲቀጥል አርማው ግን በባለሙያ ተቀርጾ በጉባኤው ሊፀድቅ እንደሚገባ ገልጸዋል ::

በሌላ በኩል አቶ ዮሐንስ አሰፋ ከክልል 14 የረቂቅ ሕገ መንግሥቱ አንቀጽ 3 ንዑስ አንቀጽ 1 እና 3 ሙሉ በሙሉ እንደሚቀበሉት ከገለጹ በኋላ በሰንድቅ አላማው ላይ የብሔር / ብሔረሰቦችንና የሃይማኖቶችን እኩልነት የሚያንፀባርቅ ብሔራዊ አርማ የሚደነግገውን ንዑስ አንቀጽ 2 በመቃወም በኢትዮጵያ ብዙ



ሃይማኖቶች ስላሉ ለምሳሌም የመስቀልንና የጨረቃን ምስል አንድ ላይ ለማስቀመጥ የሚያስብ አርቲስት ሊኖር እንደማይችልና የዚህ ዓይነቱን አርማም በሰደቅ አላማው እንዲቀመጥ መደንገጉ ሕዝብን መናቅ እንደሆነ ገልጸዋል ::

ቀጥሎም አቶ ዳንኤል በላይነህ ከክልል 14 የኢትዮጵያ ባንዲራ ሕዝቦቿ በብሔር / ብሔረሰብ ሳይለያይ የጠላት ባንዲራ በሀገሪቱ እንዳይውለበለብ ደማቸውን አፍስሰው አጥንታቸውን ከስክሰው ለዚህ ትውልድ ያስተላለፉት ታሪካዊ ቅርስ በመሆኑ ከጨቋኝ ሥርዓቶችና ባለሥልጣኖቻቸው ጋር ሊያያዝ እንደማይገባ የብሔር /ብሔረሰቦችም መብት የሚከበረውም በተግባር እንጂ በባንዲራው ላይ ተቀርጾ በሚቀመጥ አርማ እንዳልሆነ አመልክተዋል ::

አክለውም በኢትዮጵያ ያሉት ሃይማኖቶች በርካታ እንደመሆናቸው መጠን ሁሉንም ሃይማኖቶች የሚያንፀባርቅ አርማ በባንዲራው ከተቀመጠ ባንዲራው የተለያዩ ሃይማኖቶች ምልክቶች ስለሚገኙበት እያንዳንዱ ሃይማኖት ከራሱ ምልክት ውጭ ያለበትን ያገሩ ባንዲራ ለመስቀል እንደማይፈልግ ፣ ሰጣናዊ ሃይማኖትም እየተስፋፋ ስለሆነ ለእሱም ዕውቅና መስጠት እንደሚሆን አስረድተዋል ::

ከዚህም ሌላ በዝባዥች ለጭፍጨፋ ዘመቻ ሲንቀሳቀሱ ባንዲራውን ማውለበላቸው ግልጽ ቢሆንም ባንዲራው በራሱ አነሳሽነት ስላልተንቀሳቀሰና ሲጨፈጭፉም ስላልጨፈጨፈ ወንጀለኛ እንዳልሆነ ፣ ትናንት በባንዲራው ስም በደል ያደረሱ ወንጀለኞች ዛሬ በባንዲራው ሥር ፍርዳቸውን እንደሚቀበሉ ፣ የብሔር / ብሔረሰቦችና ሃይማኖቶች እኩልነት የሚያንፀባርቅ አርማ በባንዲራው ላይ ቢቀመጥ እኩልነቱን የማያከብር አመራር ካለ ሊከበር እንደማይችል እንዲሁም በረቂቅ ሕገ መንግሥቱ እርሳቸው ባወያዩባቸው ቀበሌዎች በባንዲራ ላይ አርማ ይቀመጥ የሚል አስተያየት በጭራሽ ከሕዝቡ አለመስጠቱን አቶ ዘለሌ ፀጋሥላሴ ከክልል 14 ገልጸው የፌዴራሉ ባንዲራ በአባል ክልሎች ሊውለበለብ እንደሚገባ የሚደነግግ ንዑስ አንቀጹ እንዲቀየር ሀሳብ አቅርበዋል ::

አቶ ዩሱፍ መሐመድ ከክልል 2 በበኩላቸው በባንዲራ ስም በደል የደረሰባቸው የኢትዮጵያ ሕዝቦች በደሉን ባስታወሱ ቁጥር ባንዲራውን በጥላቻ ዓይን ቢመለከቱም ቀደምት አባቶች / ሕዝቦች / ለነፃነት የተዋጉበት ምልክት መሆኑንና ጨርቅ ስለሆነ እንዳልበደላቸው ስለሚገነዘቡ እንደሚቀረቀሩለት ፣ በዘውዳዊ አገዛዝ ጊዜ በባንዲራው ላይ የነበረው መስቀል የያዘ አንበሳ እንደሆነ ፣ ያም የአንድ ሃይማኖተ የበላይነትና የዘውዱን ኃያልነት የሚያስገነዝብ እንደሆነ ፣ በደርግ ጊዜ ይህ እንደተነሳ ፣ አሁን ብሔር /ብሔረሰቦችንና ሃይማኖቶች እኩልነት የሚያንፀባርቅ ብሔራዊ አርማ

ቢደረግበትም ምንም ጉዳት እንደሌለው ገልጸው በዚህም ትርጉሙ ስለሚለወጥ ባንዲራው የሁሉም ዜጎች እንደሆነ ፣ ይዘቱ ግን በጉባኤው ሊጠና እንደሚችልና ቀደም ሲል በባንዲራው ላይ ኑሮ ምልክት ይታከልበት ያሉትን ሀሳብ እንደሳቡ ጠቁመዋል ::

አቶ አብዱልከሪም አህመድ ከክልል 5 በሰጡት አስተያየት ጉባኤው የኢትዮጵያ ታሪክ እንዴት ነበር ? በሚለው ሳይሆን ፌዴራላዊት ኢትዮጵያ እንዴት ትገንባ ? በሚለው ላይ ሊያተኩር እንደሚገባ ፣ ባንዲራው ምን ዓይነት መሆን አለበት ለሚለው ከብሔር / ብሔረሰቦች ስብጥር አንድ ኮሚቴ ተቋቁሞ ለጉባኤው የውሳኔ ሀሳብ እንዲያቀርብ ቢደረግ እንደሚሻል ከገለጹ በኋላ ባለፉት ሥርዓቶች በባንዲራው ስም በባሌ ሕዝብ ላይ የደረሰው ጭፍጨፋ በደቡብ አፍሪካ በጥቁሮች ላይ ከተደረጉ ጭፍጨፋዎች የባሰ እንደሆነ ፣ ባንዲራው አባቶቻችን ደማቸውን አፍስሰው አጥንታቸውን ከስክሰው ያቆዩት ቅርስ ነው በሚል አቶ ዳንኤል የሰነዘሩት ሀሳብ " በጦር ከወጋህ ይልቅ ጠሩን የሚሰብቅብህ ይብሳል :: " እንደሚለው የሶማሊኛ ተረት እንደማይደግፉት ፣ ሀሳቡም ለፌዴራላዊት ኢትዮጵያ ሰላም የማይበጅ በመሆኑ አቅራቢው የወከላቸውን ሕዝብ ቢያማክሩ እንደሚሻል ገልጸዋል ::

ከዚያም አቶ ደረጀ ዳኬንቶ ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል ለአንድ ባንዲራ መውለብለብ የሕዝቦች መኖር ወሳኝ በመሆኑ ሕዝቦች ሊመለኩና ሊከበሩ እንደሚገባ ሕዝቦችም ባንዲራቸው ሕልውናቸውን እኩልነታቸውንና ነፃነታቸውን የሚያረጋግጥ መሆኑን ማመን እንዳለባቸው የኢትዮጵያ ባንዲራ ለዘመናት ያቆዩትም የሌላውን ባንዲራ አውርደው የራሳቸውን በመስቀል ፣ የሌላውን አስተዳደር አፍርሰው የራሳቸውን አስተዳደር በተኩ አባቶቻችን በሚባሉ በዝባዦች ሳይሆን የበዝባዦችን ጭቆና በትከሻቸው ተሸክመው የቆዩት የኢትዮጵያ ጭቁን ሕዝቦችና ብሔር / ብሔረሰቦች እንደሆነ አመልክተዋል ::

አያይዘውም ኢትዮጵያ በውጭ ወራሪ ኃይል ስትጠቃ ጭቁን ሕዝቦቿ ያለበቂ ስንቅና ትጥቅ እስከ መጨረሻው ለባንዲራቸው ሲሉ ሲዋደቁና በጠላት ሲታረዱ ዛሬ አባቶቻችን እየተባለ የሚተረክላቸው በዝባዦች ወደ ውጭ ሀገር ፈርጥጠው እንደነበር ፣ በድል ማግሥት ለድል ያበቃቸውን ጭቁን ሕዝብ ሲጨቁኑና ሲረግጡ እንደነበር ፣ አባቶቻችን እየተባለ የሚነገርላቸው በዝባዦች ለአገሪቱ ነፃነትና ለባንዲራዋ ክብር ያደረጉት አስተዋጽኦ እንደሌለ አስታውቀዋል ::



አክለውም ዕውነታኛው ታሪክ ይህ ሆኖ ሳለ የኢትዮጵያ ሕዝብ የተባለለትን ብቻ ይቀበላል በሚል ባንዲራው አባቶቻችን ያቆዩት የአንድነትና የነፃነት ምልክት እንደሆነ የሚቀርበው የተሳሳተ ታሪክ በሕዝቡ ዘንድ ተቀባይነት እንደሌለው ጠቁመው የኢትዮጵያ አንድነት ከሕዝቦች ሕልውና ፣ ከብሔር / ብሔረሰቦችና ሃይማኖቶች እኩልነት ውጭ የማይታሰብ እንደሆነ ፣ ጉባኤው በባንዲራው ቀጣይነት የሚያወያየው የኢትዮጵያ ጭቁን ሕዝቦች ለነፃነታቸው የተዋጉበት በመሆኑ ከዚህ አንፃርም አዲሲቷን ኢትዮጵያ ለመገንባት እንጂ ከላይ በተጠቀሰው የተሳሳተ ታሪክ አኳያ እንዳልሆነ አስረድተዋል ::

ቀጥለውም በሰነድቅ አላው ላይ የብሔር / ብሔረሰቦችና ሃይማኖቶች እኩልነት የሚያንፀባርቅ አርማ እንደሚቀመጥበት ለማረጋገጥ በአንቀጽ 3 ንዑስ አንቀጽ 1 ላይ የሚሰነዝሩት " ቀይ ሆኖ " ከሚለው ቀጥሎ ብሔራዊ አርማ ይኖረዋል የሚል ሐረግ እንዲታከልበትና እንዲሻሻል ጠቁመው የአርማው መቀመጥ ለሀገሪቱም ሆነ ለባንዲራው ቀጣይነት ዋስትና እንደሚሆን ፣ አርማው የሃይማኖቶች እኩልነት ማንፀባረቁ ለሰጣናዊ እምነቶች ዕውቅና መስጠት ይሆናል በሚል የተሰነዘረው አስተያየት ሃይማኖት የአማኙ ዲሞክራሲያዊ መብት እንደመሆኑ መጠን ትክክል አለመሆኑን ፣ የሃይማኖቶች እኩልነት በአርማው ካልተንፀባረቀ እኩልነቱ አፍአዊ ሆኖ እንደሚቀር ገልጸው ከዚህም በተጨማሪ እያንዳንዱ የፌዴራል መንግሥት አባል አባልነቱን የሚቀበለው በራሱ ፈቃድ እስከሆነ ድረስ የፌዴራሉን ባንዲራ እንዲያውለበልብ የሚደነግግ ተጨማሪ ንዑስ አንቀጽ መቅረጽ አስፈላጊ እንደሆነ ገልጸዋል ::

በሌላ በኩል አቶ ኩማ ደመቅሳ ከክልል 4 የብሔር / ብሔረሰብ ተወካዮች ባንዲራውን በተመለከተ የምሬት አስተያየታቸውን የሚሰነዝሩት ከዚህ በፊት በባንዲራው ስም በመጨቆናቸውና በመረገጣቸው እንደሆነ ፣ አሁንም ይህ ቁስላቸው ሳይሽርና በበዳዮቻቸው ላይ የአጸፋ እርምጃ እንወስዳለን ሳይሉ የተዋረዱበትን ታሪክ አዲሲቷን ኢትዮጵያ በመገንባት ለማስተካከልና በጋራ ባንዲራ ለማውለብለብ በሚታገሉበት በአሁኑ ወቅት ቁስላቸውን የሚያስታውሷቸው አስተሳሰቦች ያለፉ ሥርዓቶችን በሚያደንቁ ቡድኖች ስለሚሰነዘሩ ለእንኝህም ያላቸውን ተቃውሞ በታሪክ ለማስመዝገብ ሲሉ መግለጻቸውን አስረድተዋል ::

አክለውም በኢትዮጵያ የሚገኙ ብሔር / ብሔረሰቦች አረንጓዴ ፣ ብጫ ፣ ቀይ የሆነው ባንዲራ እንደባንዲራቸው የሚቀበሉት ከወራሪ ኃይል ጋር ተዋግተው ነፃነታቸውን ያስከበሩበት የነፃነት ምልክት በመሆኑ ፣ እንዲሁም በዝባዦች ሲጨቁኑ

ያልጨቆነ በመሆኑና አሁን ደግሞ የራሳቸውንና የሃይማኖታቸውን እኩልነት የሚያንፀባርቅ አርማ ከተቀመጠበት ከዚህ በፊት ደርሰባቸው የነበረውን የጭቆና ታሪክ ይፋቃል ከሚል እንደሆነ ጠቁመው በረቂቁ የቀረቡትን ንውሳን አንቀጾች እንዳለ ተቀባይነት ቢያገኙ እንደሚደግፋና ቤቱም ወደ ውሳኔ ሀሳብ ቢያመራ እንደሚሻል አመልክተዋል ::

ቀጥሎም አቶ ታደሰ ካሳ ከክልል 3 ጉባኤው በትናንት ውይይቱ የኢትዮጵያ ሰንደቅ አላማ ጨርቅ ነው ሲባል ብዙ የጉባኤ አባላት እንገሸገሿቸው እንደነበረ አስታውሰው በአፄ ኃይለ ሥላሴ ዘመነ መንግሥት በ1948 ዓ.ም በወጣው ሕገ መንግሥት ምዕራፍ 8 አንቀጽ 124 "የኢትዮጵያ ሰንደቅ አላማ አረንጓዴ ፣ ብጫ ፣ ቀይ ቀለማት ያሉት ጨርቅ ነው :: " በሚል እንደተጠቀሰ ለጉባኤው አስገንዝበዋል ::

በሌላ በኩል አቶ ተስፋይ ሐጎስ ከክልል 1 በሰንደቅ አላማው የሚቀመጠው አርማ ምን መሆን እንዳለበት ለባለሙያ ሊተው እንደሚገባ ገልጸው አርማው የባንዲራው አካል መሆን እንደሚገባ የሚገልጽ ነገር በአንቀጹ ውስጥ ባለመኖሩ ይህ በአንቀጹ ሊካተት እንደሚገባ ሀሳብ አቅርበዋል ::

የጉባኤው ሊቀመንበር በበኩላቸው በባንዲራው የሚቀመጠው አርማ ሕዝቦች ሀገራቱን ለማልት ያላቸውን ፍላጎት የሚያንፀባርቅ መሆን ስላለበት " ... በአንድነት ለመኖርና ሀገራቸውን ለማልማት ያላቸውን ተስፋ ... " በሚል የአንቀጹ ንዑስ አንቀጽ 2 እንደሚሻሻል ገልጸው በአጠቃላይ አንቀጹን በተመለከተ ቤቱ ወደ ውሳኔ እንዲያመራ ያቀረቡትን ሀሳብ በቤቱ አብላጫ ድምፅ ተደግፏል ::

የጉባኤው ሊቀመንበር አያይዘውም እስከ አሁን በቤቱ ውስጥ ሲንሸራሸሩ የቆዩት ሀሳቦች የጉባኤው ዋና ፀሐፊ ጠቅለል ባለመልኩ እንዲያቀርቡ በጠየቁት መሠረት የጉባኤው ዋና ፀሐፊ ፣

1. የኢትዮጵያ ሰንደቅ አላማ ብሔር / ብሔረሰቦች በስሙ የተረገጡበትና የተጨቆኑበት ቢሆንም ራሳቸውን ከቅኝ ግዛት ወረራ ነፃ ያወጡበት የነፃነት ምልክት በመሆኑ የራሳቸውንና የሃይማኖታቸውን እኩልነት የሚያንፀባርቅ አርማ ተደርጎበት በኢትዮጵያ ባንዲራነቱ ይቀጥል ፣
2. የኢትዮጵያ ሰንደቅ አላማ የሕዝቦቹንና ብሔር / ብሔረሰቦቹን መብትና እኩልነት የተከበረበት አባቶቻችን ደማቸውን አፍስሰው አጥንታቸውን ከስክሰው ለዚህ ትውልድ ያቆዩት የኢትዮጵያ ሕዝቦች ታሪክ ቅርስና መለያ በመሆኑ ምንም ዓይነት አርማ ሳይደረግበት በኢትዮጵያ ባንዲራነቱ ይቀጥል ፣







3. የኢትዮጵያ ሰንደቅ አላማ ብሔር / ብሔረሰቦች በስሙ የተረገጡበትና የተጨቆኑበት መብታቸው የተገፈፈበት በመሆኑ ፣
   ሀ. ቀለማቱ በቀጥታ ወደታች የሚስመሩ ሆነው ነጭ አርማ ይደረግበት
   ለ. መደቡ ሙሉ በሙሉ ነጭ ሆኖ የብሔር/ብሔረሰቦችንና የሃይማኖቶችን እኩልነት የሚያንፀባርቅ አርማ ይደረግበት ፣
4. የፌዴራሉን ብሔራዊ ባንዲራ ክልሎች ከባንዲራቸው ጎን እንዲያውለበልቡ የሚደነግግ ንዑስ አንቀጽ በአንቀጹ ውስጥ ይቀረጽ ፣

የሚሉ እንደነበሩ ገልጸዋል ::

ከዚያም የጉባኤው ሊቀመንበር በእነዚህ ሀሳቦች ላይ ቤቱ ከሻይ ዕረፍት በኋላ ተወያይቶ እንደሚወስን ጠቅሰው ጉባኤው ለሻይ ዕረፍት ተስቷል ::

ከሻይ ዕረፍት በኋላ የጉባኤው ዋና ፀሐፊ አቶ አዲሱ ለገሠ ጉባኤው በመጀመሪያ በአንቀጽ 3 ላይ ከታሪክ አኳያ የተነሱትን ነጥቦችና ልዩነቶችን በሚመለከት ድምጽ እንዲሰጥበት ማቅረባቸውን ጠቁመው በዚህ ላይ ከሕግ አማካሪዎችና ከሌሎች ሰዎች በዕረፍት ሰዓት አስተያየት ጠይቀው በመነሻነት ያስቀመጧቸውን ነገሮች በቃለጉባኤና በቴፕ የተቀረጸ ስለሆነ በተለይ ከታሪክ አኳያ የተነሳውን እዚህ አስቀምጠን ድምፅ ከሰጠንበት ትርጉም ሆኖ ስለሚቀመጥና የጉባኤውን ሕግ የማፅደቅ ሚና ለውጦ ተርጓሚ ስለሚያደርገው ይህን እንደ መንደርደሪያ አስፍረን በአንቀጹ ንዑስ አንቀጾች ላይ ብቻ በድምፅ ብንወስን የተሻለ ነው የሚል ሀሳብ አቅርበዋል ::

ቀጥሎም የጉባኤው ሊቀመንበር ዶ/ር ነጋሶ ጊዳዳ ትናንት ከቀረቡት ሀሳቦች አንዱ ባንዲራው ጭረሽ ተለውጦና ኅብረ ቀለማቱ ቁልቁል ሆነው ነጭ ቀለም እንዲኖርበት የሚል እንደሆነና ይህን ሀሳብ ያቀረቡት አቶ አሊ አብዲ ኢሴ ከክልል 5 ስለዚህ ጉዳይ ሀሳብ ማቅረብ እንደሚፈልጉ ገልጸው ዕድሉን ለእርሳቸው ሰጥተዋል ::

አቶ አሊ አብዲ ኢሴ ከክልል 5 በዚህ ጉዳይ ላይ ብዙ የጉባኤ አባላት ሀሳብ እንዳቀረቡ ጠቅሰው ትናንት ያቀረቡት ሀሳብ መሳባቸውን ገልጸዋል ::

ቀጥለውም ከሶማሌ ብሔረሰብ ኡጋል ቪዳድ የተባሉ ታዋቂ የነበሩ ሰው ከዕለታት አንድ ቀን ሽረሪት በአፍንጫቸው ላይ በማለፏ ብዙ እንደጮኹ ሰዎችም የሚያስፈራ እንዳልሆነና መጮኽ እንደሌለባቸው ቢገልጹላቸው "እኔን የሚያስፈራኝ ያረፈብኝ ሸረሪት አይደለም ፣ ይህ አፍንጫዬ የሌሎች አራዊትና እንስሳት መተላለፊያ እንዳይሆን ሰግቼ ነው :: " ብለው እንደመለሱ ገልጸው ሰውዬውን ሰዎች እንደፈሪ ቢያይዋቸውም እሳቸው እንደሰላም ጀግና እንደሚቆጥሯቸው አስገንዝበዋል

አያይዘውም የኢትዮጵያ ብሔር /ብሔረሰቦች ባንዲራው ጨርቅ መሆኑን መገንዘብ እንዳለባቸው ፣ ሆኖም አስጊውና አጠያያቂው ባንዲራው ሳይሆን ከእሱ በስተጀርባ ያለው አስተሳሰብ እንደሆነ ጠቅሰው ሰንደቅ አላማው ከተነካ ይረክሳል ተብሎ የቀረበው ሀሳብ በመቃወም የብሔር / ብሔረሰቦችንና የሃይማኖቶችን እኩልነት የሚያመለክት አርማ እንዲታከልበት አሳስበዋል ።

ከዚያም የጉባኤው ሊቀመንበር የኢትዮጵያ ባንዲራ ተቀይሮ ቀለማቱ ቁልቁል ሆነው ነጭ ይታከልበት በሚል ቀርቦ የነበረው ሀሳብ መሳቡን ጠቁመው በአንቀጽ 3 ንዑሳን አንቀጾች ላይ የቀረቡትን ሀሳቦች በማቅረብ በድምፅ መወሰን እንደሚገባ አመልክተዋል ።

በዚህም መሠረት በአንድ በኩል የኢትዮጵያ ሰንደቅ አላማ የኢትዮጵያ ነፃነት የሕዝቦች አንድነትና የኢትዮጵያ ታሪክ ምልክት ስለሆነ ንዑስ አንቀጽ 1 ምንም ጭማሪ ሳይደረግበት እንዳለ ይቀመጥ የሚል ሀሳብ ፣ በሌላ በኩል ደግሞ የወደፊቷን ዲሞክራሲያዊት ኢትዮጵያ ለመገንባት ባንዲራው የበፊቱን ጭቆና ፣ ብዝበዛና የመሳሰሉትን ስለሚያስታውስ እነዚህን መርሳት እንዲቻል ባንዲራው ላይ የብሔሮች ብሔረሰቦች ፣ ሕዝቦችና ሃይማኖቶች እኩልነትን የሚያሳይ ብሔራዊ አርማ መታከል አለበት የሚል ሀሳብ መቅረቡን አብራርተዋል ።

አያይዘውም አንቀጽ 3 ንዑስ አንቀጽ 1 " የኢትዮጵያ ሰንደቅ አላማ ከላይ አረንጓዴ ፣ ከመሐል ብጫ ፣ ከታች ቀይ ሆኖ በመሐሉ ብሔራዊ አርማ ይኖረዋል ። ሦስቱም ቀለማት እኩል ሆነው በአግድም ይቀመጣሉ ። " ተብሎ እንዲሻሻል የቀረበውን የውሳኔ ሀሳብ ከሚደግፉት አንድ ፣ ይህንን ከሚቃወሙት መካካል ደግሞ አንድ ሰው አስተያየት መስጠት እንደሚችል አስታውቀዋል ።

በዚህም መሠረት ውሳኔ ሀሳቡን በመቃወም አቶ አዳሙ ደገፉ ከክልል 14 ይህ ባንዲራ ኢትዮጵያን በዓለምም ሆነ በአፍሪካ ያስተዋወቀ ፣ እስከ አሁን ድረስ ታሪኳን ወግዋን በመያዝ እዚህ ያደረሰና ለኢትዮጵያ ሕዝብ ባለውለታ እንደሆነ ፣ ምንም እንኳን ሰዎች በባንዲራው ስም ግፍ ሠርተዋል ቢባልም ሰዎች እና ሥራቸው እንዲጠየቁበትና በታሪክም እንዲወቀሱበት እንጂ የኢትዮጵያ ሕዝብ መኩሪያ የአንድነት ምልክት የሆነው ባንዲራ ሊወቀስና ሊጠላ እንደማይገባ ገልጸዋል ።

አያይዘውም ባንዲራው ብሔር / ብሔረሰቦች ፣ ሕዝቦችና ሃይማኖቶችን ሳይለይ በኢትዮጵያዊነታቸው አኩርቶ ከዚህ ማድረሱን ጠቁመው እስከ አሁን በነበረው አረንጓዴ ፣ ብጫ ፣ ቀይ ቀለማቱ ላይ ሌላ ነገር መጨመር እንደሌለበት የመረጣቸው የወረዳ 11 ሕዝብና የእሳቸውም አቋም እንደሆነ አመልክተዋል ።



በሌላ በኩል አቶ ደረጀ ዳኬሳ ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል ባንዲራው ላይ ብሔራዊ አርማ መታከል እንዳለበት በአንቀጽ 3 ንዑስ አንቀጽ 1 ላይ መጠቀስ እንዳለበት ያነሱትን ሀሳብና የጉባኤው ሊቀመንበር ያቀረቡትን የውሳኔ ሀሳብ እንደሚደግፉ ዶ/ር አብዱልመጂድ ሁሴን ከክልል 5 ጠቁመው በባንዲራው ስም የተፈጸመው ግፍ በአቶ አብዱልከሪም አህመድ ከክልል 5 እና በሐጂ አህመድ ሐጂ መንዞሮ ከክልል 4 እንደተገለጸና አሳዛኝ እንደሆነ እነዚህ ተወካዮች ባንዲራው ያስከተለውን ችግር ቢዘረዝሩም በመጨረሻ ሁሉም ለወደፊት በእኩልነት የሚያምን ከሆነ ብሔር / ብሔረሰቦች አንድ ላይ ሆነው የወደፊቱን በመቀየስ ሁሉንም ወደ መስማማት / ኮምፖርሚይዝ / የሚወስደውን መንገድ እንደሚመርጡ መግለጻቸውን ጠቅሰው በአንዳንድ ሰዎች ባንዲራው ላይ ምንም ነገር አይታከል አይቀነስም የሚባል ከሆነ አቶ አሊ አብዲ ኢሴ ከክልል 5 በትናንትናው ዕለት እንደገለጹት ጨርሶ የሚለወጥበት ሁኔታ እንደሚመጣ አስገንዝበዋል ።

አክለውም ኢትዮጵያ በዓለም አቀፍ ደረጃ የታወቀችው አሁን ባለው ባንዲራ ብቻ ሳይሆን በአፄ ኃይለ ሥላሴ ዘመነ መንግሥት በነበረውና አንበሳው ዘውድና መስቀልን ይዞ ከመካከል የተቀመጠበት ባንዲራ ጭምር መሆኑ ፣ አሁን ያለውን ባንዲራ ሳንተው ሁላችንንም የሚያግባባን ብሔራዊ አርማ ጨምረን አብረን እንንዛለን ብለው በብዙ ሚሊዮን በሚቆጠረው ሕዝብ የተወከሉት የጉባኤ አባላት ሲጠይቁ አይቻልም የሚል ሀሳብ ከመጣ ብሔር / ብሔረሰቦች ይህን ባንዲራ እንዲተዉት የሚገፋፋ መሆኑን ፣ ማንኛውም በኢትዮጵያ የሚገኝ ብሔር / ብሔረሰብና ሕዝብ ከቁጥር አትገባም ዝቅተኛ / እናሳ / ነህ ሳይባል በመፈቃቀርና በአንድነት መኖር እንደሚገባ ፣ ለምሳሌ በሶማሌ ክልል 38 ንዑሳን ብሔረሰብ ወይም ጎሳዎች እንዳሉና አንዱን ትልቅ ሌላውን ትንሽ አድርጎ ማንም እንደማይናገር ይህ በኢትዮጵያ ሊኖር እንደሚገባው ገልጸዋል ።

በመጨረሻም አንቀጽ 3 ንዑስ አንቀጽ 1 "የኢትዮጵያ ሰንደቅ አላማ ከላይ አረንጓዴ ፣ ከመሐል ብጫ ፣ ከታች ቀይ ሆኖ በመሀሉ ብሔራዊ አርማ ይኖረዋል ። ሦስቱም ቀለማት እኩል ሆነው በአግድም ይቀመጣሉ ።" በሚል እንዲሻሻል ለድምፅ ቀርቦ 506 ድጋፍ ፣ 4 ተቃውሞ ፣ 12 ድምፀ ተአቅቦ ተመዝግቦ ንዑስ አንቀጹ በተሻሻለው መልኩ እንዲቀመጥ ተወስኗል ።

ከዚያም የጉባኤው ሊቀመንበር በአንቀጽ 3 ንዑስ አንቀጽ 1 ላይ ብሔራዊ አርማ እንዲጨመርበት ጉባኤው ስለወሰነ አንቀጽ 3 ንዑስ አንቀጽ 2 የሚገልጸው

ብሔራዊ አርማው ምን ምን ነገሮችን እንደሚያካትት አስረድተው የንዑስ አንቀጹን መግባት ከሚቃወሙ አንድ ፣ ከሚደግፉ አንድ አስተያየት እንደሚቀበለ ገልጸዋል ::

በዚህም መሠረት አቶ ዳንኤል በላይነህ ከክልል 14 "የብሔራዊ አርማው የብሔር / ብሔረሰቦችን ፣ የሕዝቦችንና ሃይማኖቶችን እኩልነት የሚያንፀባርቅ ይሆናል ::" የተባለውን የተቃወሙበትን ምክንያት ሲገልጹ የሃይማኖትም ፣ የብሔር / ብሔረሰብ እኩልነት በተግባር መታየት አለበት እንጂ በባንዲራው መስፈር እንደሌለበት ፣ የብሔር / ብሔረሰቦችና የሃይማኖቶች እኩልነት በአርማ ሆኖ በባንዲራው ላይ ከሠፈረ የሚቀጥለው ሂደት ባንዲራውን ማፍረስ እንደሆነና በዚህም የተነሳ ሀሳቡን እንደማይቀበሉት አመልክተዋል ::

በሌላ በኩል አቶ ማሞ ጎዴቦ ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል የብሔራዊ አርማው የብሔር / ብሔረሰቦችንና ሃይማኖቶችን መካተቱን በመደገፍ በኢትዮጵያ ከሁሉም በላይ ቅድሚያ መታየት ያለበት የኢትዮጵያ ሕዝብ እንጂ አገርና ባንዲራ እንዳልሆነ ከሕዝብ ከሌለ አገር ሆነ ባንዲራ ሊኖር እንደማይችል ገልጸው በአንቀጽ 3 ንዑስ አንቀጽ 2 ላይ የተጠቀሰው የብሔር / ብሔረሰቦች ፣ ሕዝቦችና ሃይማኖቶች እኩልነት እስከሆነ ድረስ መቀመጥ ያለበትና የወከላቸውም ሕዝብ አቋም እንደሆነ አስገንዝበዋል ::

ቀጥሎም አንቀጽ 3 ንዑስ አንቀጽ 2 "ከሰንደቅ አላማው ላይ የሚቀመጠው ብሔራዊ አርማ የኢትዮጵያ ብሔር / ብሔረሰቦች ፣ ሕዝቦች እና ሃይማኖቶች በእኩልነትና በአንድነት ለመኖር ያላቸውን ተስፋ የሚያንፀባርቅ ይሆናል :: " የሚለው ለድምፅ ቀርቦ 517 ድጋፍ ፣ 4 ተቃውሞ ፣ 4 ድምፀ ተአቅቦ ተመዝግቦ ንዑስ አንቀጹ በረቂቅ ሕገ መንግሥቱ ባለበት መልኩ እንዲቀመጥ ተወስኗል ::

ከዚያም የጉባኤው ሊቀመንበር በአንቀጽ 3 ንዑስ አንቀጽ 3 ላይ የተቃውሞ ሀሳብ ካለ እንዲቀርብ የጠየቁ ባለመኖሩ ንዑስ አንቀጹ ለድምጽ ቀርቦ 520 ድጋፍ ፣ 1 ድምፀ ተአቅቦ ተመዝግቦ ያለምንም ተቃውሞ ንዑስ አንቀጹ ተቀባይነት አግኝቷል ::

ቀጥሎም የጉባኤው ሊቀመንበር አንቀጽ 3 ንዑስ አንቀጽ 4 ሆኖ "የፌዴራሉ አባሎች ከራሳቸው ባንዲራ ጎን የፌዴራሉን ባንዲራ መስቀል አለባቸው ::" የሚል ሀሳብ ከአቶ ዘለሌ ፀጋሥላሴ ከክልል 14 ቀርቦ እንደነበር ገልጸው ሀሳቡን አቶ ዘለሌ ፀጋሥላሴ እንዲያብራሩት ጠይቀዋል ::



በዚህም መሠረት አቶ ዘለሌ ፀጋሥላሴ በኢትዮጵያ ያሉት ክልሎች ተሰባስበው ፌዴራላዊ ዲሞክራሲያዊ ሪፐብሊክ ኢትዮጵያን እንዲመሠርቱና ክልሎች በፌዴራል መዋቅር የየራሳቸው ባንዲራ ስላላቸው ከራሳቸው ባንዲራ ጎን ለጎን የፌዴራሉን ባንዲራ መስቀል እንዳለባቸው በሕገ መንግሥቱ እንዲካተት በመፈለግ ሀሳቡን እንዳቀረቡት አስገንዝበዋል ::

ቀጥሎም ከላይ በተገለጸው የውሳኔ ሀሳብ ላይ አንድ የድጋፍ ፣ አንድ የተቃውሞ አስተያየት የቀረበ ሲሆን ሀሳቡን በመደገፍ አቶ ዳንኤል በላይነህ ከክልል 14 በሰጡት አስተያየት ክልሎች / ፌዴራል ስቴትስ / የራሳቸውን ጉዳይ ራሳቸው ያስተዳድራሉ እንጂ ከአገሪቱ ተለይተው የማይታዩ በመሆናቸው የፌዴራል መንግሥቱን ባንዲራ ከክልሎች ባንዲራ ጎን ለጎን መስቀል እንዳለባቸው ፣ ይህም የአገሪቷ ክፍሎች እንደሆኑ እንደሚያረጋግጥ አብራርተዋል ::

በሌላ በኩል የውሳኔ ሀሳቡን በመቃወም አንድ የጉባኤ አባል በሰጡት አስተያየት አንቀጽ 3 ንዑስ አንቀጽ 4 ሆኖ ይገባ የተባለው ሀሳብ የሰንደቅ አላማውን አሰቃቀልና አጠቃቀም በተመለከተ ሌላ ዝርዝር ሕግ እንደሚያስፈልገው ፣ ለምሳሌም የክልሎች ባንዲራ ከፍ ይበል ፣ በቀኝ ይሁን በግራ የሚሉት በሕግ መውጣት እንዳለባቸው ገልጸው ያፀደቅነው ሰንደቅ አላማ በመላ አገሪቱ የሚውለበለብ መሆኑን ግን ከአንቀጹ መንፈስ መረዳት ስለሚቻል ሌላ ተጨማሪ ንዑስ አንቀጽ ማስገባት እንደማያስፈልግ አስገንዝበዋል ::

ከዚያም የጉባኤው ሊቀመንበር በአንቀጽ 3 ንዑስ አንቀጽ 4 ሆኖ "የፌዴራሉ አባሎች ከራሳቸው ባንዲራ ጎን ለጎን የፌደራሉን ባንዲራ መስቀል አለባቸው :: " በአንቀጽ 3 ንዑስ አንቀጽ 4 ሆኖ እንዲገባ የሚለው ለድምፅ አቅርበውት 5 ድጋፍ ፣ 517 ተቃውሞ ፣ 8 ድምፀ ተአቅቦ ተመዝግቦ ተቀባይነት ሳያገኝ ቀርቷል ::

ቀጥሎም አቶ ሙሉጌታ ገ/ሕይወት ከክልል 1 አሁን ያፀደቅነው ባንዲራ 4 ነገሮችን የያዘ ስለሆነ በተለይ ብሔራዊ አርማው ከሚይዛቸው አጠቃላይ ይዘቶች ውጪ እንዳልተወሰነ ጠቁመው አጠቃላይ ይዘቶችን በመከተል በርካታ አርማዎች ለውድድር ቀርበው የሕዝብ ተወካዮች ምክር ቤት ከመረጠ በየጊዜው አርማውን የመቀያየር ሁኔታ ሊያስከትል እንደሚችል ፣ ይህም እንዳይሆንና ባንዲራው በሕገ መንግሥቱ መወሰን ስላለበት መካተት ያለባቸው ነገሮች ሁሉ በግልጽ ቀርበው እንዲወሰን ወይም ስለ ጉዳዩ ከባለሙያዎች ሀሳብ ቀርቦ ችግር የማያስከትል መሆኑ እንዲረጋገጥ አሳስበዋል ::

ለዚህም የጉባኤው ሊቀመንበር በሰጡት ምላሽ ስለባንዲራው ጉዳይ አንቀጽ በአንቀጽ የውሳኔ ድምፅ ከመስጠቱ በፊት ጉባኤው በበቂ ሁኔታ እንደተወያየበት

ገልጸው ውይይቱ እንዲቆም በአብላጫ ድምፅ መወሰኑን ፣ አሁንም በዝርዝር በንዑሳን አንቀጾች ላይ ድምፅ ተሰጥቶበት ካበቃ በኋላ እንደገና ጉዳዩን ማየት እንደሚይቻል አስገንዝበዋል ::

በሌላ በኩል አቶ አስፋው ቀኖ ከክልል 4 የባንዲራውን ቀለሞች ትርጉም በሚመለከት ግልጽ ስላልሆነላቸው እንዲብራራላቸው ስለጠየቁ አቶ ዓለምሰገድ ገ/አምላክ ከክልል 1 በሕዝብ የሚመረጠው ቋሚ መንግሥት ሊፍቀው እንደሚችልና በአንቀጹ ላይ ጉባኤው በበቂ ሁኔታ ተወያይቶ በንዑሳን አንቀጾቹ ላይ ሲወሰን እንደቆየ ገልጸው ጉባኤው በአንቀጹ በአጠቃላይ እንዲወስን አሳስበዋል ::

በዚህም መሠረት የጉባኤው ሊቀመንበር አንቀጽ 3 ከነማሻሻያው ጋር በአጠቃላይ እንዲጸድቅ ለድምፅ አቅርበዉት 513 ድጋፍ ፣ 4 ተቃውሞ ፣ 5 ድምፀ ተአቅቦ ተመዝግቦ አንቀጽ 3 ቤቱ አፅድቆታል ::

ቀጥሎም የጉባኤው ሊቀመንበር ውይይቱ በአንቀጽ 4 " የኢትዮጵያ ብሔራዊ መዝሙር " በሚለው ላይ እንደሚቀጥል ጠቅሰው አንቀጹን በንባብ አሰምተዋል ::

በዚሁ መሠረትም አቶ ደበበ አበራ ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል በአንቀጽ 4 ላይ የተቀመጡት በሕገ መንግሥቱ የሰፈሩትትን ዓላማዎችና መርሆዎች ፣ የኢትዮጵያ ብሔር / ብሔረሰቦች በዲሞክራሲያዊ ሥርዓት አብሮ ለመኖር ያላቸውን ዕምነት ፣ የወደፊት የጋራ ዕድላቸውን የሚያንፀባርቅና መሠረታዊ ነጥቦችን የያዘ እንደሆነ አስረድተዋል ::

አያይዘውም ብሔራዊ መዝሙሩ በእነዚህ ላይ ተመሥርቶ ከመጣ የኢትዮጵያ ሕዝቦች ወደፊት አገራቸውን በጋራ ለመገንባት ያላቸውን ዕምነት የሚያንፀባርቅና ኢትዮጵያዊነታቸውን የሚያጎለብት ፣ በፍላጎትና በመፈቃቀር በጋራ ጥቅም ላይ የተመሠረተ አንድነት ፈጥረው የሚኖሩ ሕዝቦች መሆናቸውን የሚያበስር እንደሚሆን ገልጸዋል ::

አክለውም የኢትዮጵያ ሕዝቦች መዝሙሩ የእኛ ነው ብለው ዕምነት የሚጥሉበት እንደሚሆን ገልጸው ዝርዝሩ በሕግ ይወሰናል የሚለው ጉባኤው ግጥም አወዳድሮ ፣ ዜማ ተቀናብሮ እስኪመጣ ስለማይጠብቅ ለዚህ ሲባል ለወደፊቱ ዝርዝር የአፈጻጸም ሕጎችን የሚመለከትና አቀማመጡም በተገቢ ሁኔታ እንደሆነ አብራርተዋል ::

ከዚያም አቶ ይገዙ እሸቴ ከክልል 3 በበኩላቸው በቀዳማዊ ኃይለ ሥላሴና በደርግ መንግሥት የነበሩት መዝሙሮች የገዢዎችን ፍላጎት የሚያንፀባርቁ እንደነበሩ ፣ አሁን ግን በረቂቅ ሕገ መንግሥቱ የቀረበው የብሔራዊ መዝሙር ይዘት የሕዝቦችን የጋራ ጥቅም ፣ ሕዝቦች በአንድነት ለመኖር ያላቸውን ዕምነት ፣



የሕገ መንግሥቱ ዓላማዎችን የሚያንፀባርቅ እንደሆነ አመልክተው ቤቱ እንዲያፀድቀው ሀሳብ አቅርበዋል ::

ቀጥሎም ፕሮፌሰር ጀማል አብዱልቃድር ከክልል 4 "በሕግ ይወሰናል" ሲባል የሚወስነው አካል ማን ነው ? በማለት ከጠየቁ በኋላ "... የወደፊት የጋራ ዕድላቸውን የሚያንፀባርቅ ይሆናል :: " በሚል አንቀጹ እንዲሻሻልና "በሕግ ይወሰናል" የሚለው እንዲወጣ ቢደረግ የሚል ሀሳብ አቅርበዋል ::

በሌላ በኩልም አቶ ተስፋይ ሐጎስ ከክልል 1 ጉባኤው መዝሙሩን ለማውጣት ውክልና የሚሰጠው ለማን ነው ? ውክልናውን የሚሰጠው ለሕዝብ ተወካዮች ምክር ቤት ከሆነ ሌላ አዲስ የሕዝብ ተወካዮች ምክር ቤት ሲመረጥ ሊቀይረው ይችላል ወይ ? መዝሙሩ እስከ መቼ ድረስ ያገለግላል ? የሚሉ ጥያቄዎችን አቅርበዋል ::

ለእነዚህም ጥያቄዎች አቶ አህመዲን ኢብራሂም ከክልል 4 በሰጡት ምላሽ " ወደፊት በሕግ ይወሰናል " ሲል በዝርዝር ሕግ ይወሰናል ማለት ከሆነ የሚወስነውም በሕዝብ ተወካዮች ምክር ቤት መሆኑን ፣ እነርሱም እንደዚህ ጉባኤተኛ የሕዝብ ተመራጮች ስለሆኑ በሕዝብ ስም መወሰን እንደሚችሉ ሁሉጊዜ ይቀያየራል ማለት ባይቻልም አስፈላጊ ሆኖ ካገኘው አዲሱ የሕዝብ ተወካዮች ምክር ቤት ሊለውጠው እንደሚችል ሆኖም ማሳመኛ ነጥብ ከሌለው እንደማያሻሽለው አብራርተዋል ::

በሌላ በኩል አቶ አዳሙ ደገፉ ከክልል 14 ይህ ጉባኤ የሀገሪቱን ሕገ መንግሥት የመቅረጽ ኃላፊነት እንዳለበት ፣ ወደፊት የሚመረጠው የሕዝብ ተወካዮች ምክር ቤት አንቀጹን ይወስነዋል ከተባለ ጉባኤው ይህንን ውክልና እንዲሰጥ የሚያደርገው ምክንያት እንደሌለ ገልጸው በውክልና ይወሰን ከሚባል አንቀጹ ቢሰረዝ እንደሚሻል አመልክተዋል ::

ቀጥሎም አንድ የጉባኤ አባል የብሔራዊ መዝሙሩ ይዘት በሕገ መንግሥቱ መካተት እንዳለበት ፣ ያለበለዚያ ግን ቀጥሎ የሚመጣው መንግሥት የመሰለውን ይዘት በመዝሙሩ በማስገባት የኢትዮጵያ ብሔራዊ መዝሙር ነው ማለት ስለሌለበት ሕገ መንግሥቱ ይዘቱን በሙሉ እንዲያካትትና ሥጋታቸውን እንዲዘጋ አሳስበዋል ::

ሌላው አንድ የጉባኤ አባል ደግሞ በሕገ መንግሥቱ ውስጥ ዝርዝር ሕግ ማካተት እንደማይቻልና በሕገ መንግሥቱ መሠረት ሌሎች ዝርዝር ሕጎች በሕግ አውጪው አካል እንደሚወጡ አብራርተዋል ::

አያይዘውም ሁሉም ነገር በሕገ መንግሥቱ እናስቀመጥ ከተባለ ሕገ መንግሥትነቱ ይቀርና ዝርዝር ሕግ እንደሚሆን ጠቁመው በአንቀጽ 4 ላይ የተቀመጠው በበቂ ሁኔታ የብሔራዊ መዝሙሩን ይዘት እንዳካተተና በሕግ

ይወሰናል መባሉም አሁን እዚህ ሊጠቃለል ስለማይችል አግባብ እንደሆነ አስረድተዋል ።

ከዚያም አቶ ደስታ ቁናሳ ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል በበኩላቸው የብሔራዊው መዝሙር ይዘት የሕገ መንግሥቱን ዓላማዎች ፣ የሕዝቦች አብሮ የመኖር ዕምነትና የወደፊት ዕድላቸውን የሚያንፀባርቅ መሆኑን ጠቁመው እነዚህ ይዘቶች በመዝሙሩ እንዴት እንደሚገለጹ እንደማይታወቅ ፣ ይህም በመሆኑ በዝርዝር በሕገ መንግሥቱ ሊካተቱ እንደሚገባ አለበለዚያ ግን ረቂቅ ሕገ መንግሥቱ ሲዘጋጅ ያዘጋጀው ክፍል የኢትዮጵያ ብሔራዊ መዝሙርንም ማዘጋጀት እንደነበረበት ፣ የጉባኤው አባላት የመጡት ሕገ መንግሥቱን ለማፅደቅ ሆኖ ሳለ አንዳንድ ነገሮችን በሕግ ይወሰናሉ በሚል ጉባኤው ሥልጣኑን አሳልፎ መስጠት እንደሌለበት ፣ አርማው ምን ዓይነት እንደሆነ መታወቅ ሲገባው መታለፉን አመልክተዋል ።

ቀጥሉም አቶ ዓለምሰገድ ገ/አምላክ ከክልል 1 አንቀጽ 4 በግልጽ የተቀመጠ ስለሆነ ፣ በሕግ ይወሰናል ከተባለ አንቀጹን በሙሉ እናውጣው የሚል ሀሳብ መቅረቡን ፣ መዝሙሩ ምን ይዘት ማካተት እንዳለበት መመሪያ መቀመጡን ፣ ውክልናም መስጠቱን አመልክተው እንዳለ እናውጣው ከተባለ ሕግ ለሚያወጣ መመሪያ ሳይሰጥ ዝም ብሎ መተው እንደሚሆን አስገንዝበዋል ።

አያይዘውም የመዝሙሩ ይዘትን በተመለከተ የተቀመጡት መመሪያዎችን ሲገልጹ የሕገ መንግሥቱን ዓላማዎች ፣ የኢትዮጵያ ሕዝቦች በዲሞክራሲያዊ ሥርዓት አብሮ ለመኖር ያላቸውን ዕምነትና የወደፊቱ የጋራ ዕድላቸውን የሚያንፀባርቅ የሚሉት እንደሆኑ አብራርተው ሕግ አውጪው አካል ከእነዚህ መመሪያዎች ውጭ ሌላ መዝሙር እንዳያወጣ ሕገ መንግሥቱ እየደነገገ መሆኑን አስረድተዋል ።

አክለውም አንቀጽ 4 እንዴት እንደሚፈጸም የተቀመጠ ስለሆነ እንሰርዘው የሚለው ሀሳብ አግባብ እንደማይመስላቸው ጠቁመው በሕግ ይወሰናል የሚለው መኖር የለበትም እኛ ሁሉን እንጨርሰው ተብሎ የቀረበውን ሀሳብ ሲመልሱም በሕግ ይወሰናል የሚል በአንቀጽ 4 ብቻ የተቀመጠ ቢሆንም ቢወጣ አስቸጋሪ እንደማይሆን ፣ ሆኖም ጉባኤው ከ ሀ እስከ ፐ ያሉ ዝርዝር ነገሮችን ሊያፀድቅ ስለማይችል አጠቃላይ መርሆዎችን አስቀምጦ ለሕግ አውጪው አካል ውክልና የመስጠት ሁኔታ እንደሚኖር ፣ ሕገ መንግሥቱም እንደ ሕገ መንግሥትነቱ አጠቃላይ መርሆዎችን ከማስቀመጥ አልፎ ዝርዝር ጉዳዮችን ሊያካትት እንደማይገባው አብራርተዋል ።



አቶ ዓለምሰገድ ገ/አምላክ ማብራሪያቸውን በመቀጠል ዝርዝር ጉዳዮችን የሚወስነው ማን ነው ? የሚል ጥያቄ መነሳቱን ጠቁመው ሁሉም ክልሎች አብረው የመሠረቱት የፌዴራል መንግስት መዝሙር ስለሆነ የሚወስነው በፌዴሬሉ የሕዝብ ተወካዮች ምክር ቤት እንደሆነ ፣ ለምሳሌ አንቀጽ 3 ንዑስ አንቀጽ 3 "የፌዴራሉ አባሎች የየራሳቸው ባንዲራና አርማ ሊኖራቸው ይችላል ። ዝርዝሩን የራሳቸው ምክር ቤት ይወስናል ።" እንደሚል ፣ በሌላ በኩል አቶ ሙሉጌታ ገ/ሕይወት መዝሙሩን የፌዴራሉ የሕዝብ ተወካዮች ምክር ቤት የሚያወጣው ከሆነ የምክር ቤቱ አባላት በተወሰኑ ዓመታት በተቀየሩ ቁጥር መዝሙሩ ሊለውጥ ነው ወይ ? በማለት ያቀረቡት ሥጋት ተገቢ እንደሆነ ፣ ያ ሥጋት ግን እንዳይመጣ የምናስቀምጠው ነገር ሌላ ችግር እንዳያመጣ ጥንቃቄ ማድረግ እንደሚገባ ፣ አንዴ ከወጣ በኋላ በየጊዜው መለወጥ የለበትም ከተባለም ምናልባት የመጀመሪያው ምክር ቤት መዝሙሩ ወይም አርማውን ሲያወጣ ግድፈት ቢፈጽምና ሌላው ለማስተካከል ቢፈልግ እንደማያግድ ፣ መሻሻሉ የሚያመጣውን ጥቅምና ጉዳት መዝኖ ብቻ እንደሚሻሻል አስገንዝበው ያ ምክር ቤትም የሕዝብ ተወካይ ስለሆነ ሥጋቱ ቀርቶ ጉባኤው አንቀጹ በተቀመጠው መልኩ እንዲያፀድቀው ጠይቀዋል ።

ቀጥሉም አቶ ዮሐንስ አሰፋ ከክልል 14 አንቀጽ 4 "የኢትዮጵያ ብሔራዊ መዝሙር የሕገ መንግሥቱን ዓላማዎችና የኢትዮጵያ ሕዝቦች በዲሞክራሲ ሥርዓት አብረው ለመኖር ያላቸውን ዕምነት እንዲሁም አንድነታቸውን ፣ ጀግንነታቸውን የሚያንጸባርቅ ሆኖ በሕግ ይወሰናል ።" ጉባኤው የመዝሙሩን ግጥምና ዜማ ሊያወጣ ስለማይችል የቋሚው መንግሥት የሕዝብ ተወካዮች ምክር ቤት እንዲያስፈጽመው ፣ የሚል ማሻሻያ ሀሳብ አቅርበዋል ።

ከዚያም የጉባኤው ሊቀመንበር አራት ሀሳቦች በአንቀጽ 4 ላይ እንደተነሱ እነዚህም ፣

- አንድነት የሚል ቃል ይታከልበት ፣
- በአንቀጹ የሕግ አውጪው አካል በግልጽ ይቀመጥ ፡
- ጉባኤው የመዝሙሩን ይዘት ተመልክቶ አንቀጹን ማፅደቅ አለበት ፣
- በረቂቅ ሕገ መንግሥቱ የተቀመጠውን እንዳለ እንቀበለው ፣

የሚሉ መሆናቸውን ገልጸዋል ።

ከዚያም አቶ ሙሉጌታ ገ/ሕይወት ከክልል 1 ሕገ መንግሥቱን ለማሻሻል የተቀመጠ አንቀጽ ስላለና ሥጋታቸውን አቶ ዓለምሰገድ ገ/አምላክ በአደረጉት ገለጻ ስለተወገደ ሀሳባቸውን እንደሳቡ ገልጸዋል ::

ሆኖም የአቶ ሙሉጌታ ገ/ሕይወት ሀሳብ ደግፈው ሲናገሩ የነበሩት ጉባኤተኞች ሀሳባቸውን ስላላነሱ በቤቱ ከላይ የተሰነዘሩት ሀሳቦች እንዳሉ መሆናቸውን የጉባኤው ሊቀመንበር አመልክተዋል ::

ቀጥሎም ዶ/ር አብዱልመጂድ ሁሴን ከክልል 5 አንቀጽ 4 በረቂቅ ሕገ መንግሥቱ በተቀመው መልኩ ድምፅ እንዲሰጥበት የውሳኔ ሀሳብ አቅርበው አንድነት የሚል ቃል ይግባ ያሉት የጉባኤ አባል "... አብሮ ለመኖር... " በሚለው ሊካተት ስለሚችል ከዚህ አኳያ እንዲያዩት አሳስበዋል ::

ከዚያም በውሳኔ ሀሳቡ ላይ የድጋፍና የተቃውሞ አስተያየት እንዲሰጥበት ሊቀመንበሩ ስለጠየቁ አቶ አባይ ፀሐዬ ከክልል 1 ጉዳዩ በድምፅ እንዲወሰን ይቅረብና ይሻሻል ከተባለ ምን ምን ማሻሻያዎች ወደ ሚለው እንዲመጣ በቀጥታ አንቀጹ ባለው መልኩ ይቀመጥ የሚለው ለድምጽ እንዲቀርብ አሳስበዋል ::

በሌላ በኩል አቶ አዳሙ ደገፉ ከክልል 14 እርሳቸው ያቀረቡት ሀሳብ ለምን በውሳኔ ሀሳብነት እንዳልቀረበ ጠይቀው ሳይጠየቁ እንዲሁ ሀሳቡ መቅረቱ አግባብ እንዳልሆነ አመልክተዋል ::

በመጨረሻም ዶ/ር አብዱልመጂድ ሁሴን ያቀረቡት የውሳኔ ሀሳብ ለድምፅ ይቅረብ የሚለውን አብዛኛው የጉባኤ አባል ስለደገፈው ለድምፅ ቀርቦ አንቀጽ 4 በቀረበው መልኩ እንዳለ እንቀበለው የሚለው ድጋፍ 515 ፣ ተቃውሞ 3 ፣ ድምፀ ተአቅቦ 10 ተመዝግቦ አንቀጽ 4 በረቂቅ ሕገ መንግሥቱ ላይ በተቀመጠው መልኩ ተቀባይነት አግኝቶ ጉባኤው የዕለቱን ውይይት ከቀኑ 7:35 ሰዓት አጠናቋል ::



ኅዳር 1 ቀን 1987 ዓ.ም በ3:05 ሰዓት በሕገ መንግሥት ጉባኤ አዳራሽ የተካሄደው የኢትዮጵያ ሕገ መንግሥት ጉባኤ ስብሰባ የተመራው በጉባኤው ሊቀመንበሩ በዶ/ር ነጋሶ ጊዳዳ ሲሆን በቅድሚያ የጉባኤው ዋና ፀሐፊ አቶ አዲሱ ለገሠ በዕለቱ 528 የጉባኤ አባላት ስላሉ ተጨማሪ አባላት የገቡ ስለሆነ ውይይቱን መጀመር እንደሚቻል አስታውቀዋል ::

ከዚያም ሊቀመንበሩ የጉባኤው ውይይት የሚቀጥለው በረቂቅ ሕገ መንግሥቱ ከዚያም በሚለው ላይ እንደሆነ ጠቅሰው በውስጡ የተካተቱትን 3 አንቀጽ 5 "ስለቋንቋ" በሚለው ላይ እንደሆነ ጠቅሰው በውስጡ የተካተቱትን 3 ንዑስ አንቀጾች በንባብ አሰምተው በአጠቃላይ በርዕሱ ሆነ በንዑስ አንቀጾቹ ላይ አስተያየት ካለ እንዲቀርብ አሳስበዋል ::

በዚህም መሠረት አቶ መሐመድ አህመድ ከክልል 3 የሁሉም የብሔር /ብሔረሰቦች ቋንቋ በዕኩልነት ዕውቅና ማግኘታቸው በጣም እንደሚያስደስት ፣ ከሌሎች ብሔር / ብሔረሰቦች ቋንቋዎች አማርኛ በተሻለ ደረጃ ስለሆነ የፌዴራሉ የሥራ ቋንቋ መሆኑ ተቀባይነት እንዳለው ፣ የፌዴራሉ አባሎች የየራሳቸው የሥራ ቋንቋ እንዲኖራቸው መደረጉም አስፈላጊ እንደሆነ ጠቅሰው የአንቀጹ ርዕስ ስለቋንቋ ስለሚል መጀመሪያ ሁሉም ቋንቋዎች እኩል መሆናቸውን ማረጋገጥ ስለሚገባ ንዑስ አንቀጽ 1 እና 2 ቦታዎች ቢለዋወጡ እንደሚሻል ሀሳብ አቅርበዋል ::

በሌላ በኩል ደግሞ ዶ/ር አረጋዊ አክሊሉ ከክልል 1 በአንቀጽ 5 የሠፈረው ድንጋጌ ለብዙ ዘመናት በኢትዮጵያ ብሔር / ብሔረሰቦና ሕዝቦች ላይ የነበረውን የቋንቋ ልዩነትና ከዚያ ጋርም የተያያዘውን ማህበራዊ ፣ ፖለቲካዊና ኢኮኖሚያዊ ችግር እንደሚያስወግድ ፣ ባለፉት ሥርዓቶች ግን ሕዝቦች በራሳቸው ቋንቋ እንዳይግባቡና እንዳይማሩ ከፍተኛ አድሎ ይደረግባቸው እንደነበር ፣ ስለዚህ የቋንቋዎች ዕድገት የተገደበበት ፣ ሰዎች የራሳቸውን ቋንቋ ለመጠቀም የሚያፍሩበት ፣ ለቋንቋዎች የወፍ ቋንቋና የመሳሰሉ ስሞች እየተሰጠ ተናጋሪዎቹ የሚተረጉምላቸው ይዘው ይቀርቡበት የነበረበት ጊዜ እንደነበር አስታውሰው አሁን የቀረበው አንቀጽ ግን የቋንቋዎችን ዕድገት ሁኔታ ሚዛናዊ የሚያደርግ በመሆኑ አንቀጹ ሙሉ በሙሉ እንደሚቀበሉትና የንዑስ አንቀጽ 1 እና 2 አቀማመጥም ባለበት ቢሆን ምንም ችግር እንደሌለው አስተያየት ሰንዝረዋል ::

በማስከተልም አቶ ኢብራሂም ሱሌማን ከክልል 4 ቋንቋ የሰው ልጅ በተግባር መግለገያነት መሥራት ከጀመረበት ጊዜ ጀምሮ የተገለገለበት የመግባቢያ መሣሪያ ሲሆን በኢትዮጵያ ቋንቋዎች ከዚህ የተለየ እንዳልሆኑ ፣ በመሆኑም በኢትዮጵያ ብዙ ቋንቋዎች የሚገኙ ሲሆን ከእነዚህ ውስጥ በታሪክ አጋጣሚ አማርኛ ከሌሎች የበለጠ ለማደግ ዕድል እንዳገኘ ፣ ቋንቋ የተግባር መገልገያ መሣሪያ በመሆኑ ማንኛውም ሰው ይበልጥ የሚያውቀው አፉን የፈታበትን ቋንቋ እንደሆነ ፣ በኢትዮጵያ ብቻ ሳይሆን በሌሎችም አገሮች አንዱ ቋንቋ ከሌላው የበለጠ ዕድል ማግኘቱ በታሪክ የተረጋገጠ መሆኑን ፣ ለምሳሌ የአረብኛ ቋንቋ የእስልምና ሃይማኖት መሪ ነብዩ መሐመድ የሚናገሩት ቋንቋ በመሆኑ ከሁሉም ቋንቋዎች በበለጠ በዓለም ላይ ለመስፋፋት መቻሉን እንዲሁም እንግሊዝኛ ፣ ፈረንሳይኛና የስፓኒሽ ቋንቋዎች ተነጋሪዎቹ አገሮች ሌሎችን አገሮች በቅኝ ግዛት በመያዛቸው ከሌሎች ቋንቋዎች የበለጠ እንደተስፋፉ ገልጸዋል ።

አያይዘውም የአማርኛ ቋንቋ በአገሪቱ ውስጥ ከሌሎች ቋንቋዎች የበለጠ ለመስፋፋት የቻለው በተለይ በዛጉዌ ዘመነ መንግሥት ከ1264 -1270 ዓ.ም ባለው ጊዜ ውስጥ በቤተ መንግሥት በሥራ ላይ በማዋል ሲሆን በ1270 ዓ.ም የዛጉዌ ሥርወ መንግሥት ወድቆ በምትኩ በአንዳንድ ታሪክ ፀሐፊዎች የአማራ ሥርወ መንግሥት የሚባለው ሰለሞናዊው ሥርወ መንግሥት በይኩኖ አምላክ አማካይነት ሥልጣን በያዘበት ጊዜ የአማርኛ ቋንቋ የመስፋፋት ዕድል በጣም ጎልቶ መታየት እንደጀመረ ፣ በተለይም በዚያን ጊዜ የቋንቋው መስፋፋት የተወሰነው በወሎ ክፍለ ሀገር ሲሆን በኃላ ፣ በሲዳሞና በዳሞት ቋንቋዎች ላይ ጫና እያስከተለ መኖሩንና በዚህ ሁኔታ ለብዙ ዓመታት በአከባቢው ተወስኖ እንደቆየ ጠቁመዋል ።

በተጨማሪም ለአማርኛ ቋንቋ መስፋፋት ከፍተኛ ዕድል የተፈጠረው በአፄ ሚንሊክ ዘመነ መንግሥት በተለይ በ1879 ዓ.ም ፊንፊኔን ዋና ከተማ በማድረግ የግዛት ማስፋፋት ዘመቻ ከተከፈተበት ጊዜ አንስቶ እንደሆነ ፣ አፄ ሚንሊክ ወደ ምሥራቅ ፣ ደቡብ ፣ ምዕራብና ደቡብ ምሥራቅ ባደረጉት የግዛት ማስፋፋት ዘመቻ በተመቀሱት ቦታዎች ያሰፈሯቸው በአዝማችነት አብረዋቸው የዘመቱትና በየግዛቱ 28 ገባር ተቆጥሮ የተሰጣቸው ነፍጠኞች እንደነበሩ ፣ በመሆኑም አንድ ሰው ከገዢው መደብ በተለይም ከነፍጠኞች ጋር ለመግባባትና ለመኖር በግዴታ የአማርኛን ቋንቋ ማወቅ ስላለበት የብሔረሰቡ ተወላጆች በተለይም የቀድሞው ባላባቶችና አባት ኢላዎች እንዲሁም ባለሌላ ማዕረጎች ልጆቻቸውን እስለ ጎጃም ድረስ እየላኩ የአማርኛ ቋንቋ እንዲማሩ ያደርጉ እንደነበር አመልክተዋል ።



አክለውም በአፄ ሚንሊክ ዘመነ መንግሥት የአማርኛ ቋንቋ በመግባቢያነት ብቻ ተወስኖ ከፊውዳሉ ገዢ መደቦች ጋር ለመግባባት የሚጠቅም እንደነበረና በአፄ ኃይለ ሥላሴ ዘመነ መንግሥት ግን በትምህርት ቤቶች ውስጥ የአማርኛ ቋንቋ በሰፊው እንደተሰጠ ፣ በዚህም ወቅት መጀመሪያ የተማሩ ማዕረግ እንዳገኙና በኋላ ግን በ1960ዎቹና በ1970ዎቹ አካባቢ በተቋሞች ፣ በኮሌጆችና በዩኒቨርሲቲ የሚያስተምሩ ትምክህተኛ መምህራን በአማርኛ ቋንቋ የሚመራሩና አማርኛ ቋንቋን እየሰባበሩ ለመማር የሚፈልጉትን የሌሎች ብሔረሰብ ተማሪዎች ማጥላላት እንደጀመሩ ፣ በዚህም አሠራር ተማሪዎች እየተሰደቡ በመካከላቸው መቃቃርና መናናቅ እንደተከሰተ ፣ ሆኖም ይህ ሂደት የአማርኛ ቋንቋን በደንብ የማይችሉ የነበሩት አጣርተው ለመናገር እንደረዳቸውና የራሳቸውን ቋንቋም ዞር ብለው ለመመልከት እንደረዳቸው ጠቅሰው በደርግ ጊዜ የነበረውም ከኃይለ ሥላሴ ከነበረው ያልተለየ መሆኑን አስረድተዋል ።

አያይዘውም በሽግግር መንግሥቱ ወቅት የቋንቋ ጉዳይ ሲታይ የአማርኛ ቋንቋ ለማዕከላዊ መንግሥት በሥራ ቋንቋነት እያገለገለ ፣ ክልሎች ደግሞ በራሳቸው ቋንቋ እየተጠቀሙ እንደሆነ ከሽግግሩ መንግሥት ለክልሎች የሚተላለፉ መመሪያዎች በአማርኛ ቋንቋ እንደሆነ ፣ ለወደፊቱ የሚመሠረተው አሠራር ከዚህ የተለየ መሆን እንደሌለበት ፣ ስለዚህ ያለፉትንና አሁን ያለውን በመመልከት ለወደፊቱ የአማርኛ ቋንቋ የፌዴራሉ መንግሥት የሥራ ቋንቋ ሆኖ እንዲቀጥልና የሌሎች ቋንቋዎችም የመስፋፋት ዕድል የተጠበቀ ሆኖ በሕገ መንግሥቱ ቢካተት ጠቃሚ ነው የሚል አስተያየት ሰንዝረዋል ።

ቀጥሎም አቶ ማርቆስ ሊራንጎ ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል አማርኛ ቋንቋ ያደገው ሌሎች ብሔር / ብሔረሰቦች ቋንቋቸውን በመጥላት ወይም ቋንቋዎች እንዳያድጉ በሕግ ተደንግጎ ሳይሆን በተለይ 45 ብሔር/ ብሔረሰቦች ያሉባት የደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል በቋንቋቸው ላይ በደረሰ ጫናና ግፍ ምክንያት ለስደት እንደተዳረጉ ፣ ከአማርኛ የተለየ ቋንቋ ተናጋሪ የሆኑ ብሔር/ብሔረሰቦች አባላት የተለያየ የስድብና የንቀት ስያሜዎች ይደርስባቸው እንደነበርና አማርኛ የግድ እንዲማሩ ለማድረግ ጫናና ስቃይ እንደነበር ጠቁመዋል ።

ቋንቋ መግባቢያ እንጂ በራሱ ዕውቀት እንዳልሆነና ምንም እንኳን የገዢ መደቦች ይሰጡት የነበረው ትርጉም የተለየ ቢሆንም የማንም ብሔር / ብሔረሰብ ቋንቋ ከሌላው የማይበልጥ ወይም የማያንስ መሆኑን ፣ ይህም ሁኔታ ሁሉም ብሔር / ብሔረሰብ በአፍ መፍቻ ቋንቋው በማስተማር ፣ ቋንቋውን በፍርድ ቤትና በሌሎች የክልል ሥራዎች በመጠቀም በተጨባጭ እያየው መሆኑን ፣ ስለዚህ በአማርኛ መግባባቱ ጥሩ ቢሆንም በአማርኛ ተናገር ተብሎ እንደማይገደድ ግን

እንደሚያውቀው ፣ አማርኛ ከሌሎች ቋንቋዎች የበለጠ ስላደገ የፌዴራሉን የሥራ ቋንቋ ከእሱ ውጭ ለማድረግ መሞከር ተገቢ ስለማይሆንና የተሻለ አማራጭ ለማግኘት ቢጋራ መግባባት ስለማይቻል የፌዴራሉ መንግሥት የሥራ ቋንቋ መሆኑ እንደሚቀበሉት ፣ በየብሔር / ብሔረሰቡ ደግሞ ቋንቋና ባህል ማሳደግ እንደሚያስፈልግ ጠቁመው አንቀጽ 5 ንዑስ አንቀጽ 1 እንዳለ እንዲሆን ሀሳብ አቅርበዋል ።

አክለውም በንዑስ አንቀጽ 3 ላይ የፌዴራሉ አባሎች የየራሳቸው የሥራ ቋንቋ በሕግ እንደሚወስን ቢገለጽም ለምሳሌ የደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል በክልልነቱ የፌዴራሉ አባል ቢሆንም በውስጡ የተለያዩ ቋንቋዎች የሚናገሩ ከ45 በላይ ብሔረሰቦች እንዳሉ ፣ የሥራ ቋንቋቸውም እንደ የዞኑና ብሔረሰቡ ተግባራዊ እየሆነ መሆኑን ፣ ስለዚህ በፌዴራሉ አባልነት እንደ ደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል ሳይሆን እንደ ብሔረሰብም የሚጠቀሙ ስለመሆናቸው መጥቀስ ስለሚያስፈልግ ንዑስ አንቀጽ 2 " ማናቸውም የኢትዮጵያ ቋንቋዎች በመግባቢያነት ፣ በሥራ ፣ በትምህርትና በዳኝነት በእኩልነት የመንግሥት ዕውቅና ይኖራቸዋል ።" በሚል ተዘርዝሮ እንዲሻሻል ንዑስ አንቀጽ 3 ግን እንዳለ እንዲሆን ሀሳብ አቅርበዋል ።

ከዚያም አቶ ተመስገን ማሞ ከክልል 14 በአገራችን እስከ 250 የሚደርሱ ቋንቋዎች አሉ ተብሎ እንደሚነገር ፣ ቋንቋ መነጋገሪያ ፣ መግባቢያ ፣ ሀሳብ መግለጫና መልዕክት ማስተላለፊያ እንደሆነ ፣ ቋንቋ የመነጋገሪያና ራሱን ችሎ ፊደላት ኑረውት በፊደላት አማካይነት ሀሳቡን የሚያስተላልፍበት ብሎ በሁለት መክፈል እንደሚቻል ፣ አንድን ቋንቋ ብሔራዊ ከሚያሰኙት ውስጥ አንዱ የራሱ ፊደላት ኑረውት በፊደሎቹ በመጠቀም ሀሳቡን በፅሑፍ ማስተላለፍ ሲችል ሲሆን ሌላው ደግሞ ከፍተኛ የቋንቋው ተጠቃሚ ሲኖር መሆኑን ፣ ምናልባት አንዳንድ ቋንቋዎችን ከገዢ መደብ ሥርዓት ጋር ሲያያዙ ቋንቋዎችን የግድ እንዲማሩ የተደረገበት ወቅት እንደነበር ፣ ሆኖም አንድ ቋንቋ ብሔራዊ ነው ሲባል ቋንቋውን ከነበረው ሥርዓት ጋር ማያያዝ እንደሌለበትና በአሁኑ ወቅት የዓለም መግባቢያ የሚሆነው ቋንቋ ለምሳሌ እንግሊዝኛ ለመማር ራስን በግድ የመገፋፋት ሁኔታ እንዳለ ጠቁመው ከብሔራዊ ቋንቋ መሥፈርት አንፃር አንቀጽ 5 ንዑስ አንቀጽ 1 አማርኛ ብሔራዊ ቋንቋ ሊሆን ይገባዋል ተብሎ ሊገባ እንደሚችል ፣ በአብዛኛው ብሔር / ብሔረሰቦች ተብለው የተለዩት በቋንቋቸው ስለሆነ ቋንቋቸውንና ባህላቸውን ማስፋፋት እንዲችሉ በንዑስ አንቀጽ 2 የተደነገገው ተገቢ እንደሆነ ፣



የፌዴራሉ አባሎች አመሠራረትም በቋንቋ ላይ የተመሠረተ በመሆኑ በራሳቸው ቋንቋ የመሥራት ዕድል እንዲያገኙ ማድረግ ተቀዳሚ ሊሆን ስለሚገባው ንዑስ አንቀጽ 3 እንደሚያስፈልግና በአጠቃላይ በአንቀጽ 5 የተካተቱ ንዑስ አንቀጾች እንዳሉ እንዲቀመጡ አሳስበዋል ።

ቀጥሎም አንድ የጉባኤ አባል እያንዳንዱ ቋንቋ ለማህበረሰቡ በመግባቢያነት የሚያገለግል በመሆኑ ሁሉም ቋንቋዎች እኩል እንደሆኑ ፣ በአገራችን ግን ባለፉት ሥርዓቶች ቋንቋዎች ሁሉ በእኩልነት ሲታዩ እንዳልቆዩ ፣ በተለይ የአማርኛ ቋንቋ የማይናገሩ ሲሰቃዩ ፣ ፍርድ ሳያገኙና መግባባት ሳይችሉ መቆየታቸውንና ብሔራዊ ቋንቋን ባለማወቅ በ6ኛ ፣ በ8ኛ ፣ 12ኛ ክፍል የመውደቅ ሁኔታ እንደነበረ ፣ በተለይ በክልል 5 በቋንቋ በኩል ከፍተኛ ችግር እንደነበረ ለምሳሌ ከ1ኛ ደረጃ እስከ ዩኒቨርሲቲ በነበረው ሂደት ትምህርትን ለመከታተል በመቸገር ያለመማር ወይም ስደት እንደነበር ፣ ከሌላ ብሔረሰብ ዩኒቨርሲቲ የሚመጡ የሚሰደቡና የሚናቁበት ሁኔታ እንደነበር ፣ በመሆኑም ቋንቋው ከነበረው ኢ-ዲሞክራሲያዊ አፋኝ ሥርዓት ጋር የተቆራኘ እንደነበረ ፣ ለምሳሌ በ1969 ዓ.ም የሱማሊኛ ቋንቋ በላቲን ፊደል በድብቅ ይጻፍ እንደነበርና ሲጻጻፉም ከተያዙ ይታሰሩ እንደነበር ፣ በፍርድ ቤት አስተርጓሚ እንዳልነበር ፣ ስለዚህ አማርኛ ያደገው ሌሎችን ቋንቋዎች በመግደል እንደሆነ ፣ ከዚህም አኳያ የቋንቋ ጥያቄ የዲሞክራሲ ጥያቄ እንደሆነና በተማሪዎች እንቅስቃሴም እንደነበር ፣ይህ ሁኔታ በሕዝቦች ትግል እልባት አግኝቶ ባለፉት ሦስት ዓመታት እያንዳንዱ ብሔር / ብሔረሰብ ራሱን እንዲያስተዳድር ሲደረግ በራሱ ቋንቋ እንዲዳኝ ፣ እንዲማርና ልምምድ በማድረግ ቋንቋውን እንዲያሳድግ ማስቻሉን አስታውቀዋል ።

አክለውም በአንቀጽ 5 ንዑስ አንቀጽ 2 የተቀመጠው የኢትዮጵያ ብሔር / ብሔረሰቦች ባደረጉት ትግል ባለፉት ሦስት ዓመታት ያገኙትን መብትና የቋንቋ እኩልነት በተጨማሪም ብሔር / ብሔረሰቦች በአካባቢያቸው የራሳቸውን ቋንቋ እንዲጠቀሙ የሚያረጋግጥ ስለሆነና የአንቀጹ ርዕስ "ስለቋንቋ" ስለሚል በቅድሚያ የቋንቋ እኩልነት ያልነበረበት ሥርዓትን ማስወገዱን ማስረገጥ ስለሚያስፈልግ ንዑስ አንቀጽ 2 ሊቀድም እንደሚገባ ፣ በተጨማሪም በፌዴራሉ ውስጥ የመግባቢያ ቋንቋ ስለሚያስፈልግና በታሪክ አጋጣሚ የአማርኛ ቋንቋ ያደገና ለሥራ ምቹ ሁኔታ የፈጠረ ስለሆነ አማርኛ የፌዴራሉ መንግሥት የሥራ ቋንቋ እንደሚሆን የሚገልጸው ንዑስ አንቀጽ 1 ንዑስ አንቀጽ 2 እንዲሆንና አንቀጹ ግን ባለበት መልኩ እንዲቀመጥ የሚል አስተያየት አቅርበዋል ።

ከዚያም አቶ ሙሉጌታ አመና ከክልል 4 ቋንቋ ሊያድግ የሚችለው የሥራ ቋንቋ ሲሆን እንዲሁም ብዙ ተናጋሪዎች ሲኖሩት እንደሆነ ጠቅሰው በኢትዮጵያ ውስጥ የተለያዩ የብሔር / ብሔረሰቦች ቋንቋዎች ቢኖሩም የአማርኛ ቋንቋ የገዢው ክፍል ቋንቋ በመሆኑ ባለፉት መቶ ዓመታት በከፍተኛ ዕድገት እምርታ በማሳየት አሁን ከደረሰበት ደረጃ ላይ መድረሱንና በሌሎች ቋንቋዎች ላይ ግን በነበረው ተፅዕኖ እንዳያድጉ መደረጉን ለምሳሌ በኦሮምኛ ክፍል ውስጥ መናገር ያስቀጣ እንደነበረ ፣ በእነዚህ ተፅዕኖዎች የተነሳ ሌሎች የማደግ ዕድል ስላላገኙ አሁንም ቢሆን አማርኛን በመንግሥት የሥራ ቋንቋነት የግድ መቀበል እንደሚገባ ገልጸዋል ::

አያይዘውም ከአማርኛ ቋንቋ ውጭ ሌሎቹ እስከ አሁን ድረስ ተረስተውና ተረግጠው ስለቆዩ የመንግሥት ዕውቅና ብቻ ማግኘታቸው በቂ ስለማይሆን እንዲያድጉና እንዲበለጽጉ ጥናቶችና ምርምሮች መካሄድ ስላለባቸው መንግሥት ልዩ ድጋፍ የሚሰጥበትን መንገድ ማመቻቸት ስላለበት በንዑስ አንቀጽ 2 ላይ " ... የሚያድጉበትና የሚበለጽጉበት ሁኔታ እንዲመቻች መንግሥት ልዩ ትኩረትና ድጋፍ ይሰጣል :: " የሚል ሐረግ እንዲጨመርና የንዑስ አንቀጽ 1 እና 2 ቅደም ተከተል እንዲዘዋወር ሀሳብ አቅርበዋል ::

ከዚያም ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ ከክልል 14 አማርኛ የፌዴራሉ መንግሥት የሥራ ቋንቋ እንዲሆን የመቀበሉ አስፈላጊነት ቋንቋው ቀደም ብሎ ስላደገና አብዛኛው የኢትዮጵያ ሕዝብ ስለሚናገረው እንደሆነ ፣ በኃይለ ሥላሴ ዘመነ መንግሥት ከክልል 5 የተለያዩ ቦታዎች ትምህርት ቤቶች ተሠርተው የሚማር ባለመገኘቱ የተወሰኑ የአካባቢው ሰዎች ልብስ ተገዝቶላቸው ወደ አዲስ አበባ መጥተው እንደተማሩና እንጀራ መብላት እንደተለማመዱ ፣ በአካባቢው ፍርድ ቤትም የተርጓሚ ችግር እንዳልነበረና ከአማርኛ ቋንቋ ውጭ በመጻፍ የተከሰሰ ሰው እንደሌለ ፣ አፄ ኃይለ ሥላሴ ለኦሮሞና ለኦሮምኛ ቋንቋ ክብር እንደነበራቸውና የንጉሡም ሆነ የእርሳቸው የብሔረሰብ ሁኔታ ሲታይ ከኦሮሞ ጋር የመቀላቀል ሁኔታ እንደላው አውስተው የአባቶቻቸውን የዘር ሐረግ ቆጥረዋል ::

አያይዘውም እንግሊዞች አዲስ አበባ ሲገቡ ኦሮሞና አማራን ለያይተው መንግሥት ለማቋቋም ቢሞክሩም አማራና ኦሮሞ በመጋባትና በመዋለድ በመዋሀዳቸው ለመለያየት እንዳልቻሉ ፣ በመሆኑም አማራና ኦሮሞ ጠላት ሆነው እንደማያውቁ ፣ እንዲሁም አንድ መንግሥት በሌላው መንግሥት ሲተካ በደርግ ጊዜም እንደታየው ያለፈው መንግሥት እንደሚተች ጠቅሰዋል ::



አክለውም በሀገራችን ያሉት የእስልምና ሃይማኖት ተከታዮች 50% ወይም ከዚያ ጥቂት ያነሱ ስለሆነ ሃይማኖታቸውን ማወቅ ስላለባቸውና ይህንን ለማድረግ የሚችሉትም ከሌሎች ቋንቋዎች ይልቅ በአረብኛ የተጻፉትን መጻሕፍት በማንበብ ስለሆነ አብዛኛው አረቦች በአፍሪካ ስላሉ አረብኛ የአፍሪካ ቋንቋ በመሆኑና ተናጋሪዎቹ ጎረቤቶቻችን ወዳጆቻችንና በደምም የተሳሰርን እንዲሁም ዓለም አቀፍ ቋንቋ ስለሆና እንደ ሳኡዲ አረቢያና ሊቢያ ያሉት አገሮች ቋንቋውን በነፃ ለማስተማር ስለሚረዱ ማስገደድም ባይኖር በአገራችን አረብኛ የሚስፋፋበት መንገድ እንዲታሰብበት አሳስበዋል ::

ቀጥሎም አቶ ሀሰን አሊ ከክልል 4 በአንቀጽ 5 የንዑስ አንቀጽ 1 እና 2 ቦታ የመዘዋወር ጉዳይ መሠረታዊ ነገር እንዳልሆነና የሕገ መንግሥቱ ቅርጽ ኮሚቴው ዕልባት ሊደርግለት እንደሚችል ፣ እንዲሁም የፌዴራሉ መንግሥት አባላት የራሳቸውን ቋንቋ በምክር ቤታቸው የመወሰን መብት እንዳላቸው አንቀጽ 5 ንዑስ አንቀጽ 3 ስለሚገልጽና ከፌዴራሉ አባላት አንዱ የደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል በውስጡ ወደ 45 የሚገመቱ ብሔር / ብሔረሰቦች ቋንቋቸውን እንዴት እንደሚጠቀሙ ፣ ችግራቸውን እንዴት እንደሚፈቱና እንደ አንድ ክልል አብረው ሊሠሩ የሚችሉበትን ሁኔታ ምላሽ የሚሰጠው ራሱ የክልሉ ሕዝብና ምክር ቤት ስለሆነ በክልሉ ሕገ መንግሥት እንጂ አሁን በቀረበው ሕገ መንግሥት ውስጥ ባይካተት እንደሚሻል ከተካተተም ችግር እንደሚፈጥር አመልክተዋል ::

አያይዘውም ሶማሌ ልብስ መልበስና እንጀራ መብላት የማያውቅ ስለነበረ ለማስልጣን ሲባል በኃይለ ሥላሴ መንግሥት ጊዜ ወደ አዲስ አበባ አምጥቶ ማስተማር እንደነበረ ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ የተናገሩት የአቅኝነት ሂደት መሆኑንና አሁንም ከቅኝ ገዢዎች ጋር የተያያዘ አስተሳሰብ መሆኑን ከዚህ ሂደ ማምጣት የተከናወነው ንጉሡ ወደፊት የሶማሌን ሕዝብ ሰጥ ለጥ አድርጎ የሚገዛላቸው የሰው ኃይል ለማፍራትና በራሳቸው አምሳያ ለመቅረጽ እንጂ ሕዝቡ እንዲማር ቢታሰብ ኖሮ እዚያው አካባቢው በቋንቋው እንዲማር ይደረግ እንደነበር አስገንዝበዋል ::

አክለውም የኦሮሞ ሕዝብ ወይም የአማራ ሕዝብ አንዱ ሌላውን ጠላት የሆነበት ታሪክ እንደሌለ ፣ በመሆኑም የኦሮሞና የአማራ ሕዝብ ወንድማማችና ወዳጅ በመሆኑ አንዱ አንዱን እንደሚያከብር ፣ የአማራ ገዢ መደብ ግን የኦሮሞ ሕዝብና የአማራ ሕዝብ የጨቆንና የአንድን አካባቢ ባህል ፣ ቋንቋ ፣ ሥነ ልቡና በሕዝቦች .

ላይ ለመጫን የሚታገል እንደነበረ ገልጸው ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ የራሳቸውንና የኃይለ ሥላሴን ኦሮሞነት ቢቆጥሩም በስም ሳይሆን የኦሮሞነት ሥነ ልቦና ያለውና በኦሮሞነቱ የሚኮራ ፣ ቋንቋና ባህሉን የሚያከብር ፣ በብሔራዊ ማንነቱ የሚያምን እንደሆነ አመልክተዋል ።

አስከትለውም ነብዩ መሐመድ የጻፉት ዕሑፍ በአረብኛ ስለሆነ አረብኛ የእስልምና ሃይማኖትን በሚገባ ሊገልጽ እንደሚችል ፣ ሆኖም በዓለም ላይ ያሉት ከ500 ሚለዮን የሚበልጡት እስላሞች ሁሉም ቦታ አረብኛ እንደማይጠቀሙ ለምሳሌም እንዶነዢያኖች ፣ ፓኪስታኖችና ሕንዶች እስላም የሆኑት አረብኛን በመጠቀም አለመሆኑን ፣ ስለዚህም የእስልምና ሃይማኖት መስፋፋት ከአረብኛ ቋንቋ ጋር መገናኘት እንደሌለበትና ሁሉም የፌዴራሉ ምክር ቤት በአሁኑ ጊዜ ሊሠራበት የሚችለው ቋንቋ አማርኛ መሆኑን ፣ ሆኖም በብሔራዊ ቋንቋና በመንግሥት ሥራ ቋንቋ መካከል መሠረታዊ ልዩነት ስላለ በአንቀጽ 5 ንዑስ አንቀጽ 1 መደንገግ ያለበት በተቀመጠበት መልክ " አማርኛ የፌዴራል መንግሥት የሥራ ቋንቋ ይሆናል ። " በሚል እንደሆነ ጠቅሰው በጉዳዩ ላይ የተደረገው ውይይት በቂ ስለሆነ ቤቱ ወደ ድምፅ መስጠት እንዲሻገር ሀሳብ አቅርበዋል ።

ከዚያም አቶ ዓለምሰገድ ገ/አምላክ ከክልል 1 ስለቋንቋ በሕገ መንግሥቱ ሲነሳ የትኛው ቋንቋ የመንግሥት የሥራ ቋንቋ ይሁን የሚለው ከመመለሱ በፊት ባለፈው ታሪክ የቋንቋዎች እኩልነት ያልተረጋገጠ ስለነበር በቅድሚያ የቋንቋዎችን እኩልነት ማረጋገጥ ስለሚያስፈልግ አንቀጽ 5 ንዑስ አንቀጽ 1 ንዑስ አንቀጽ 2 ፣ ንዑስ አንቀጽ 2 ደግሞ ንዑስ አንቀጽ 1 ሆነው እንዲቀመጡ አሳስበዋል ።

አክለውም የቋንቋዎች በመንግሥት ዕውቅና ማግኘት ማለት በመግባቢያነት ፣ በትምህርትና በዳኝነት መስኮች ለመጠቀም እንደሚቻል ስለሚያመለክት የንዑስ አንቀጽ 2 መዘርዘር አስፈላጊ እንዳልሆነ ፣ በተጨማሪም የአንቀጹ ርዕስ ስለቋንቋ ስለሚልና የመንግሥት እገዛ ደግሞ የመንግሥት ተግባር በመሆኑ ለአናሳ ቋንቋዎች እገዛ እንደሚደረግ በመንግሥት ተግባር ላይ ካልተጠቀሰ በቦታው ላይ ሲደረስ ሊታይ የሚችል እንጂ ከአንቀጽ 5 ርዕስ ውጭ የሆነን ጉዳይ ማስገባት እንደማያፈልግ ጠቅሰዋል ።

አያይዘውም አንድ ሕዝብ ትምህርት ቤት የማይሄደው ትምህርት ቤት ሳይከፈትለት ወይም በረሀብ ምክንያት ወደ ትምህርት ቤት ለመሄድ ሳይችል እንደሆነና በክልል 5 ሕዝቡ ሳይማር የቀረው ትምህርት ቤት ተከፍቶለት አልማርም ብሎ በመቅረት ሳይሆን በነፍጠኞችና ትምክህተኞች ሥርዓት



ምክንያት መሆኑን ፣ ማንም ሕዝብ እንደ ሁኔታውና ባህሉ የራሱ ምግብና የአመጋገብ ሥርዓት እንደሚኖረው ፣ በመሆኑም ሥርዓቱ ሊከበርለት ይገባል እንጂ እንጀራ የማይበላ ያልሰለጠነ ነው ማለት እንደማይቻል ፣ የኦሮሞ ሕዝብ በባሌና በተለያዩ ቦታዎች በአፄ ኃይለ ሥላሴ መጨፍጨፉን እንደሚያውቁና ያለፈውን የነፍጠኞች አስተሳሰብ ከሌለ በስተቀር ስለሕዝቦች ከሕዝቦች የበለጠ የሚያውቅ እንደማይኖር ፣ ስለሆነም ስለክልል 5 ወይም ሶማሌ ሕዝብ የትምህርት ዕድልና ችግር ከማንም በላይ ሊናገር የሚችለው የክልል 5 ወይም የሶማሌ ሕዝብ እንደሆነ ፣ በተጨማሪም ኦሮሞ በአፄ ኃይለ ሥላሴ የተጨፈጨፈ ሆኖ ሳለ ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ ግን አፄ ኃይለ ሥላሴ ለኦሮሞ ሕዝብና ለኦሮምኛ ቋንቋ ትልቅ ክብር ነበራቸው ብለው ያውም ገፊት ቀማሽ የሆነው የኦሮሞ ተወካይ ምስክርነት ሊሰጥ በሚችልበት ጉባኤ መናገራቸው እንዲሁም ከሶማሌ ሕዝብ በላይ ሶማሌን አውቃለሁ ብለው መናገራቸው ሐቁን መካድና ማዛባት እንደሆነ አብራርተዋል ።

እንዲሁም ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ በተደጋጋሚ ሕዝቡ አኩርፏል ሲሉ ምናልባት ነፍጠኞችና ኢሠፓዎችን ለማለት እንደሆነ ፣ እርሳቸውም የሚመኙትና የሚወክሉት ሥርዓት ሊኖር እንደሚችልና ያ ሥርዓት ሊጠቀመኝ ይችላል ማለት እንደሚችሉ ፣ የእስልምና ሃይማኖት አምልኮትና እምነት እንጂ አረብኛ ቋንቋን ባለመሆኑ የኢትዮጵያ እስላሞች በአረብኛ ቁርአንን እንዲያውቁ አረብኛ በቋንቋነት ቢስፋፋ ጥሩ ነው የተባለው መነሻ ትክክል እንዳልሆነ ፣ ከዚህ አንጻር ለምሳሌ የኦሮሞ እስላም ቋንቋው ኦሮምኛ ፣ የሶማሌ እስላም ደግሞ ቋንቋው ሶማሊኛ እንደሆነና እስላም በመሆናቸው አረብ ሳይሆኑ ኢትዮጵያዊ መሆናቸውን ፣ ስለዚህ አረብኛ ብቻ ሳይሆን እንደ እንግሊዝኛና ፈረንሳይኛ ያሉ ሌሎች ቋንቋዎች ለመግባቢያነት ቢስፋፉ ጥሩ መሆኑንና ከሁሉም ቋንቋዎች አረብኛ ተለይቶ ይስፋፋ ማለት ግን ተገቢ እንዳልሆነ አመልክተዋል ።

ከዚያም የጉባኤው ሊቀመንበር ዶ/ር ነጋሶ ጊዳዳ ሥነ ሥርዓት ለማስጠበቅ ሲባል የተናጋሪውን ሀሳብ ማቆም እንደማይቻል እንዲሁም በአፄ ኃይለ ሥላሴ እና በደርግ ጊዜ መሳደብ ቀርቶ መቃወም እንኳን ከፍተኛ ቅጣት ያስከትል እንደነበር አስታውሰው አሁን ግን ሁሉም የጉባኤ አባል ሀሳቡን መግለጽ እንደሚችል አሳስበዋል ።

አያይዘውም በኃይለ ሥላሴ ዘመነ መንግሥት በኦሮሞች ላይ ምንም ግፍና ስቃይ አልነበረም ማለት ፍፁም ውሸት ብቻ ሳይሆን ከራሱ ከሕዝቡ በላይ አውቃለሁ በማለት መሳደብ መሆኑን አስገንዝበዋል ።

በተጨማሪም ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ አፄ ኃይለ ሥላሴ ኦሮሞ መሆናቸውንና የኦሮምኛ ቋንቋ ያከብሩ እንደነበረ ቢገልጹም ነሐሴ 1936 ዓ.ም የወጣው ድንጋጌ

ቁጥር 3 የሚያሳየው ግን ከአማርኛ ቋንቋ በስተቀር ሌሎች የኢትዮጵያ ቋንቋዎች የትምህርትና የመንግሥት የሥራ ቋንቋ እንዳይሆኑ የሚገልጽ መሆኑን አመልክተዋል ።

ከዚያም ቤቱ በጉዳዩ ላይ በቂ ውይይት ስላደረገበት ወደ ውሳኔ ሀሳብ እንዲሄድ የሚል ሀሳብ ለድምፅ ቀርቦ ከቤቱ 1/3ኛ በላይ በመደገፉ ቤቱ ወደ ውሳኔ ማስተላለፍ ተሸጋግሯል ።

በዚህም መሠረት አንቀጽ 5 ንዑስ አንቀጽ 1 እና 2 ቅደም ተከተላቸው እንዲዘዋወር ቤቱ የተስማማ ሲሆን ንዑስ አንቀጽ 1 በሚሆነው " ማናቸውም የኢትዮጵያ ቋንቋዎች በእኩልነት የመንግሥት ዕውቅና ይኖራቸዋል ። " በሚለው ላይ

" መንግሥት ለቋንቋዎች ዕድገት ድጋፍና ልዩ ትኩረት ያደርጋል ። " እንዲሁም ቋንቋዎች የሥራ ፣ የትምህርት ፣ የዳኝነትና የመግባቢያ መሆናቸው ያካትት ወይንስ ንዑስ አንቀጹ በተቀመጠው መልኩ በቂ ነው የሚሉ አማራጮች ለድምፅ ቀርበው ንዑስ አንቀጹ እንዳለ በተቀመጠው መልክ እንዲሆን 471 ድጋፍ ፣ 22 ተቃውሞ ፣ 8 ድምፀ ተአቅቦ ተመዝግቦ ንዑስ አንቀጹ በተቀመጠው መልክ እንዲሆን ተወስኗል ።

በመጨረሻም አንቀጽ 5 በአጠቃላይ እንዲፀድቅ ለድምፅ ቀርቦ 523 ድጋፍ ፣ 2 ተቃውሞ ፣ 1 ድምፀ ተአቅቦ ተመዝግቦ አንቀጹ ፀድቆ ጉባኤው ለሻይ ዕረፍት ተነስቷል ።

ከሻይ ዕረፍት በኋላ የጉባኤው ሊቀመንበር ዶ/ር ነጋሶ ጊዳዳ ጉባኤው ውይይቱን የሚቀጥለው በረቂቅ ሕገ መንግሥቱ አንቀጽ 6 መሆኑን ገልጸው አንቀጹን በንበብ አሰምተው በአንቀጹ ርዕስ ወይም በአንቀጹ በአጠቃላይ አስተያየት ካለ እንዲቀርብ ጠይቀዋል ።

በዚህም መሠረት አቶ ሁሴን መሐመድ ከክልል 5 የኢትዮጵያዊነት ዜግነት ከኢትዮጵያዊያን በመወለድ ፣ ኢትዮጵያ የዓለም ኅብረተሰብ አካል እንደመሆኗ ከውጭ ወደ ሀገራችን የሚገቡ የውጭ ዜጎች ኢትዮጵያውያን ለመሆን ከፈለጉ በሕጉ መሠረት የኢትዮጵያዊት ዜግነት እንደሚያገኙ ስለሚያስቀምጥ አንቀጹ ከያዛቸው 3 ንዑስ አንቀጾች ጋር እንዳለ እንዲቀመጥ ሀሳብ አቅርበዋል ።

በሌላ በኩል አቶ አቡኔ መንገሻ ከክልል 3 በአንቀጽ 6 ንዑስ አንቀጽ 2 ላይ የኢትዮጵያ ዜግነት በደም እንደሚገኝ ሲያስቀምጥ ንዑስ አንቀጽ 2 ደግሞ የውጭ አገር ዜጎች የኢትዮጵያን ዜግነት የሚያገኙበት ሁኔታ እንዳ እንደሚገልጽ ፣ በንዑስ



አንቀጽ 3 " ዜግነትን በሚመለከት ዝርዝሩ በሕግ ይወሰናል ።" የሚለው በደም የሚገኘውን የኢትዮጵያ ዜጋ የመሆን መብት እንዳይሸራረፍ በንዑስ አንቀጽ 2 መጨረሻ ላይ ዝርዝሩ " በሕግ ይወሰናል" የሚለው እንዲጨመርበትና ንዑስ አንቀጽ 3 እንዲሰረዝ ሀሳብ አቅርበዋል ።

ቀጥሎም አቶ ዑመር አብዱሰታር ከክልል 13 ንዑስ አንቀጽ 1 ወላጆቹ/ ወላጆቿ ወይም ከወላጆቹ /ከወላጆቿ አንደኛው ኢትዮጵያዊ / ኢትዮጵያዊት የሆነ /የሆነች የኢትዮጵያ ዜጋ ነው / ናት ። ሲል ነው /ናት የሚለው አባባል ኢትዮጵያዊነት በፍላጎት ላይ የተመሠረተ በፈቃደኝነት የሚገኝ ወይስ በግዳጅ የሚሰጥ መብት እንደሆነ እንዲብራራላቸው ጠይቀዋል ።

አቶ አህመዲን ኢብራሂም ከክልል 4 ዜግነት በሁለት መንገዶች እንደሚገኝ ፣ የሽውም እናቱ/ቷ ወይም አባቱ/ቷ ኢትዮጵያዊ ከሆኑ ወይም ሁለቱም ኢትዮጵያዊ ከሆኑ ልጁ ወይም ልጅቷ የኢትዮጵያ ዜግነት እንደሚያገኝ/እንደምታገኝና ይህም ዜግነት በደም የተገኘ እንደሆነ ፣ በሌላ በኩል የውጭ ዜጋ በሀገሪቱ ሕግ የተቀመጡትን መሥፈርቶች ካሟላ የኢትዮጵያ ዜግነት እንደሚሰጠው ፣ መሥፈርቶቹም ከወንጀል ነፃ መሆን ፣ ከተወሰነ ዓመት በላይ መኖር ፣ የሀገሪቱን ቋንቋ በሚገባ ማወቅ ሲሆኑ መሥፈርቶቹ እንደ የሀገሩ እንሚለያዩ አስረድተዋል ።

አያይዘውም ዜግነት የግዳጅ መብት እንዳልሆነ ፣ በረቂቅ ሕገ መንግሥቱ አንቀጽ 33 ላይ በዝርዝር እንዳለ ፣ አሜሪካ የተወለደ ልጅ እናቱና አባቱ የውጭ ዜጋ ቢሆኑም የአሜሪካዊ ዜግነት እንደሚያገኝ ፣ በኢትዮጵያ ውስጥ ግን ይህ እንደማይሠራ ፣ አንድ አሜሪካ ከሚኖር / ከምትርን ወይም ከሚኖሩ ኢትዮጵያዊያን የተወለደ / ች ልጅ ሁለት ዓይነት ዜግነት ሊኖረው / ሊኖራት እንደሚችል ፣ አማራጩ ግን ክፍት እንደሆነ አብራርተዋል ።

ቀጥሎም ፕሮፌሴር ጀማል አብዱልቃድር ከክልል 4 በአንቀጽ 6 ንዑስ አንቀጽ 1 መጀመሪያ ላይ "በዚሁ አንቀጽ ንዑስ አንቀጽ 3 የተጠቀሰው እንደተጠበቀ ሆኖ " የሚል እንዲጨመርበት ሀሳብ አቅርበው የጣምራ ዜግነት ጉዳይ የሕግ ባለሙያዎች በስፋት እንዲያብራሩት ጠይቀዋል ።

ከዚያም አቶ አብዱራዛቅ መሐመድ ከክልል 14 የአንቀጽ 6 ንዑስ አንጽ 1 አገላለጽ ሁለቱንም ፆታዎች ጎን ለጎን ማስቀመጡ ተገቢ እንደሆነና ከዚህ በፊት በሴቶች ላይ ይደርስ የነበረውን የዜግነት ችግር የሚፈታ መሆኑን ፣ የድርብ ዜግነት ጉዳይ አስፈላጊነቱ ስላልታየ በደምና በሕግ ዜግነት ማግኘት ላይ ብቻ እንደተወሰነ አብራርተዋል ።

ቀጥሎም ዶ/ር ተክተል ፎርሲዶ ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል በአንቀጽ 6 ንዑስ አንቀጽ 1 ላይ የተቀመጠው የዜግነት መብት መሆኑና ሰብአዊ መብታቸውን የሚያስጠብቅ እንጂ የጎዳጅ ሁኔታ ያለበት አለመሆኑን አስረድተዋል ።

በሌላ በኩል አቶ መኩሪያ ታፈሰ ከክልል 14 የጣምራና ዜግነት ጉዳይ በግልጽ ባለመቀመጡ ከሌሎች አገሮች አኳያ በግልጽ እንዲቀመጥ ፣ በአንቀጽ 6 ንዑስ አንቀጽ 1 ላይ ለተቀመጠው የዜግነት መብት ምን ዓይነት ማረጋገጫ እንዳለና ፓስፖርት ለማውጣት ቢጠይቅ ዜግነቱ በምን እንደሚረጋገጥ ፣ ስለዜግነት የሚወጣው ዝርዝር ሕግ ዜግነትን የሚያብራራ እንጂ መለወጥ በሚችልበት መልኩ የሚቀረጽ ለመሆኑ ምን ማረጋገጫ እንዳለ እንዲብራራ ጠይቀዋል::

አቶ አህመዲህ ኢብራሂም ከክልል 4 ጣምራ ዜግነትን አንቀጽ 6 ራሱ እንደሚፈቅድና ውጭ ያለ/ች ኢትዮጵያዊ/ት ከውጭ ዜጋ ቢወልድ/ብትወልድ የሕፃኑ/ሷ ኢትዮጵያነት የተረጋገጠ መሆኑ በጣምራ ዜግነት ሊያገኝ ወይም ልታገኝ እንደሚችል ወይም እንደምትችል ፣ ካልፈለገ/ካልፈለገች ግን አንዱን ይዞ ወይም ይዛ ሊቆይ ወይም ልትቆይ እንደሚችል ፣ የፌዴሬሽኑ አባላት ጉዳይ በተመለከተም ፌዴራል ስቴትስ የዜግነት መብት መስጠት እንደማይችሉና የፓስፖርት ጉዳይን በተመለከተ ደግሞ ማንኛውም ኢትዮጵያዊ ማግኘት እንደሚችልና ተከለከለኩ የሚል ግለሰብ በሕግ አስፈጻሚዎች በኩል መብቱን ሊያስፈጽም እንደሚችል አብራርተዋል ።

በማስከተልም የጉባኤው ዋና ፀሐፊ አቶ አዲሱ ለገሠ ፓስፖርት እንዴትና ከየትኛው ቢሮ ይሰጣል የሚለውን ስለ ክልልና ፌዴራል መንግሥታት የሥልጣን ክፍፍል ሲነሳ ጉባኤው ሊነጋገርበት እንደሚችል ፣ ከዚህ አንቀጽ ጋር ግን እንደማያገናኝ ፣ አንቀጽ 6 ንዑስ አንቀጽ የሚመለከተው ከወላጆች ሁለቱ ወይም አንዱ ኢትዮጵያዊ/ት ከሆነ/ች ልጁ/ልጅቷ የኢትዮጵያዊነት ዜግነት እንደሚኖረው/እንደሚኖራት ፣ በውጭ አገር ዜጎች ደግሞ በአንቀጽ 6 ንዑስ አንቀጽ 2 እንደገባ ገልጸው የጣምራ ዜግነት ጉዳይ ግን በግልጽ ባለመቀመጡ ቤቱ እንዲወያይበት ሀሳብ አቅርበዋል ።

ከዚያም ወ/ሮ አረጋሽ አዳነ ከክልል 1 አንቀጽ 6 ንዑስ አንቀጽ ውጭ ያሉ ኢትዮጵያዊያን ልጆቸው ከኢትዮጵያውያን ከተወለደ/ች ኢትዮጵያዊ ዜግነት ሊያገኝ/ልታገኝ እንደሚችል ወይም እንደምትችል ይህ ማለት ግን በውጭ ስለተወለደ/ች የውጭ ዜግነት ያገኝ ወይም ታገኝ ከሆነ ይህንን ያሳጣል ማለት እንዳልሆነ ግልጽ መሆን እንዳለበትና አንቀጹም ጣምራ ዜግነትን እንደሚፈቅድ አስረድተዋል ።



ቀጥሎም ፕሮፌሰር ጀማል አብዱልቃድር ከክልል 14 አንቀጽ 6 ንዑስ አንቀጽ 1 መጀመሪያ ላይ የዚህ አንቀጽ ንዑስ አንቀጽ 3 እንደተጠበቀ ሆኖ የሚል እንዲገባ አሳስበው ጣምራ ዜግነት ያለገደብ የሚሰጥ ባለመሆኑ በዝርዝር ሕግ እንደሚወሰን በአንቀጽ 6 ንዑስ አንቀጽ 1 ላይም እንዲቀመጥ ነው ሲሉ አመልክተዋል ።

ከዚያም አቶ አባይ ፀሐዬ ከክልል 1 አንቀጽ 6 ንዑስ አንቀጽ 1 ጣምራ ዜግነትን እንደሚፈቅድና ይህም በአኛ ሕግ ቢያንስ ከወላጆቹ አንዱ ኢትዮጵያዊ /ት ከሆነ/ች የኢትዮጵያዊነት ዜግነት ሊያገኝ/ ልታገኝ እንደሚችል / እንደምትችል ፣ ይህም በመሆኑ ንዑስ አንቀጽ 3 እንዳለ እንዲቀመጥና ኢትዮጵያዊ መሆን መብት መታገድ እንደሌለበት አስገንዝበዋል ።

ቀጥሎም ወ/ሮ እንወይ ገ/መድህን ከክልል 3 ደግሞ አንቀጽ 6 ንዑስ አንቀጽ 1 በ1923 ፣ በ1948 እና በ1980 የወጡት ሕገ መንግሥቶች በሴቶች ሲያደርሱት የነበረውን ውርደትና የሴቶችን የዜግነት መብት ያስጠበቀ መሆኑን ፣ የጣምራ ዜግነት ጉዳይ ከዚህ ቀደም ያልነበረ ስለሆነ ለወደፊት መኖሩ ለሴቶች የሚጠቅም ስለሆነ በአንድ ንዑስ አንቀጽ ተቀርጾ እንዲቀመጥ ትኩረት እንዲሰጠው አሳስበዋል ።

አስከትለውም የጉባኤው ዋና ፀሐፊ የጣምራ ዜግነት ጉዳይ በንዑስ አንቀጽ 1 እና 2 በደምና በሕግ የተቀመጠ መሆኑንና ለአፈጻጸም ደግሞ በዝርዝር ሕግ እንዲወሰን በንዑስ አንቀጽ 3 መኖሩን ገልጸው አንቀጹ እንዳለ ቢቀመጥ እንደሚሻል አመልክተው የተነሱትን ማሻሻያዎችን ለጉባኤው አቅርበዋል ።

አቶ አቡኔ መንገሻ ከክልል 3 አንቀጽ 6 ንዑስ አንቀጽ 3 ወደ ንዑስ አንቀጽ ውስጥ እንዲገባ ያነሱትን ሀሳብ የሳቡ ሲሆን ፕሮፌሰር ጀማል አብዱልቃድር ከክልል 4 ደግሞ ንዑስ አንቀጽ 1 እና 2 ከንዑስ አንቀጽ 3 ጋር ሆነው ቢታዩ የማንም መብት እንደማይነካ ገልጸው አንቀጹ ባለበት መልኩ ቢቀመጥ እንደማይቃወሙ አመልክተዋል ። እንዲሁም አቶ መኩሪያ ታፈሰ ከክልል 14 ጣምራ ዜግነትን በተመለከተ መወሰን ያለበት ጉባኤው መሆኑን ጠቁመው ይህንን ሥልጣኑን ለሕግ አውጪው አካል መተው እንደሌለበት ገልጸዋል ።

የጉባኤው ዋና ፀሐፊ የመርህ ጥያቄ በመሆኑ ጉባኤው በዝርዝር ሕግ ይወሰናል ብሎ ሲያስቀምጥ ፣ ወደፊት በሕዝብ ለሚወከል አካል እያስተላለፈ መሆኑን ፣ ዜግነትን በተመለከተ ዝርዝሩ በሕግ ይወሰናል የተባለው ለንዑስ አንቀጽ 1 እና 2 የሚያገለግል መሆኑን አብራርተዋል ።

ቀጥሎም አቶ ዓለምሰገድ ገ/አምላክ ከክልል 1 አንቀጹ ዜጋ ማን ነው
ለሚለው ሁለት መርሆዎችን እንዳስቀመጠና እነዚህም በንዑስ አንቀጽ 1 እና 2
እንደተጠቀሱና ከሁለቱ መርሆዎች በመነሳት ዝርዝር ሕግ እንደሚወጣ
አስረድተዋል ፡፡

በማስከተልም የጉኤባው ሊቀመንበር ጉባኤው በጉዳዩ ላይ በበቂ ተወያይቶበታል የሚለው ሀሳብ አቅርበው በጉባኤው 1/3ኛ ድምፅ በላይ በመደገፉ ጉባኤው ወደ ድምፅ መስጠቱ ተሸጋገሮ አንቀጽ 6 ንዑስ አንቀጽ 1 እንዳለ ይቀመጥ የሚለውን ድጋፍ 517 ፣ ተቃውሞ 1 ፣ ድምፅ ተአቅቦ 6 ተመዝግቦ አንቀጽ 6 ንዑስ አንቀጽ 1 ባለበት መልኩ እንዲቀመጥ ተወስኗል ፡፡ ከዚያም በአንቀጽ 6 ንዑስ አንቀጽ 2 እና 3 ላይ የማሻሻያ ሀሳብ ስላልቀረበባቸው ጉባኤው በአንቀጽ 6 በአጠቃላይ ድምፅ እንዲሰጥ ተጠይቆ ድጋፍ 516 ፣ ተቃውሚ 1 ፣ ድምፅ ተአቅቦ 5 ተመዝግቦ አንቀጽ 6 እንዳለ ፀድቋል ፡፡

ከዚያም ጉባኤው ውይይቱን በአንቀጽ 7 ላይ የቀጠለ ሲሆን አቶ ሙሉጌታ ከክልል 4 በአንቀጽ 6 ንዑስ አንቀጽ 1 ላይ ሁለቱም ፆታዎች አገላለጽ በግልፅ እንደተቀመጠ ጠቅሰው በአንቀጽ 7 በድጋሚ ለወንዱ የተገለጸው ለሴቷም እንደሚሆን ስለቀረበ ከሁለቱ አንዱ እንዲቀየር አሳስበዋል ፡፡

ቀጥሎም አቶ ታደሰ ግርሚሶ ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል ፣ አቶ ኒሐልጋች ዲንግ ከክልል 12 ፣ አቶ ግርማ ብሩ ከክልል 4 ፣ ወ/ሮ እንወይ ገ/መድህን ከክልል 3 ፣ አቶ ታሪኩ ፅጌ ከክልል 14 አንቀጽ 6 ንዑስ አንቀጽ 1 የተቀመጠው የሴቶችን የዜግነት መብት በአኩልነት ማስረገጥ በማስፈለጉ እንደሆነ ገልጸው አንቀጽ 7 በቀረበው መልኩ እንዲቀመጥ ሀሳብ አቅርበዋል ፡፡

አቶ ተስፋዬ ፊቻላ ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል ባቀረቡት ሀሳብ መሠረት ጉባኤው የሕገ መንግሥት ቅርጽ ኮሚቴ ያቋቋመ በመሆኑ የቅርጹን ሁኔታ ሊያስተካክለው እንደሚችል የጉባኤው ዋና ፀሐፊ ገልጸው አንቀጹ የገባው በሁለቱም ፆታዎች አገላለጽ ለማስቀመጥ ሲፈለግ የሚያስከትለውን መንዛዛትና ድግግሞሽ ለማስገድ እንደሆነ አመልክተዋል ፡፡

በመጨረሻም አንቀጽ 7 እንዳለ ይፅደቅ የሚለው ለድምፅ ቀርቦ ድጋፍ 520 ፣ ተቃውሚ 1 ፣ ድምፅ ተአቅቦ 1 ተመዝግቦ ጉባኤው አንቀጽ 7 እንዳለ ተቀብሉት የዕለቱ ስብሰባ ከቀኑ 7:00 ሰዓት ላይ ተጠናቋል ፡፡



ኅዳር 2 ቀን 1987 ዓ.ም ከጧቱ 3:00 ሰዓት የተጀመረውና በሕገ መንግሥት በጉባኤ አዳራሽ የተካሄደው የኢትዮጵያ ሕገ መንግሥት ጉባኤ የተመራው በጉባኤው ሊቀመንበር በዶ/ር ነጋሶ ጊዳዳ ሲሆን በቅድሚያ የጉባኤው ዋና ፀሐፊ አቶ አዲሱ ለገሠ በዕለቱ የተገኙ የጉባኤ አባላት ብዛት 525 ስለሆነ ጉባኤው ውይይቱን መጀመር እንደሚችል ባስታወቁት መሠረት ውይይቱ ተጀምሯል ፡፡

በመጀመሪያ የጉባኤው አጀንዳ በሕገ መንግሥቱ ረቂቅ ላይ የተጀመረውን ውይይት መቀጠል የሚል እንደሆነ ሊቀመንበሩ ገልጸው በምዕራፍ 2 የሕገ መንግሥት መሠረታዊ መርሆዎች በሚለው ርዕስ ሥር በአንቀጽ 8 የሕዝብ ሉዓላዊነት በሚለው ንዑስ አንቀጽ ሥር ያሉትን ሦስት አንቀጾች በንባብ ካሰሙ በኋላ በአንቀጹ ላይ አስተያየቶች እንዲቀርቡ ጠይቀዋል ፡፡

ከዚያም ሐጂ አብዱራህማን አብዱልቃድር ከክልል 13 ወደ ርዕስ ጉዳዩ ከመግባቱ በፊት ቤቱ እስከ አሁን ባያቸው 7 አንቀጾች ዲሞክራሲያዊ አካሄድ መከተሉን ገልጸው ሆኖም እናሳ ብሔረሰቦች ባለፉት ሥርዓቶች የደረሰባቸው ጭቆና መግለጽ ይችሉ ዘንድ ሰፊ ዕድል ሊሰጣቸው እንደሚገባ ፣ ከዚህ አንፃር እሳቸው እስከ አሁን በታዩት አንቀጾች ሀሳብ ለመስጠት እጅ ቢያወጡም ዕድል ሊያገኙ እንዳልቻሉና ይህም ሁኔታ መቀጠል ስለሌለበት እንዲሻሻል አሳስበዋል ፡፡

የጉባኤው ሊመንበሩ ይህንን ጉዳይ በተመለከተም በሰጡት መልስ ለመናገር ዕድል የሚሰጡት ብቻቸውን ሳይሆን ከጉባኤው ፀሐፊና ምክትል ፀሐፊ ጋር በመረዳዳት መሆኑን ፣ በተቻለ መጠን አስፈላጊ ሆኖ ሲገኝ ለእናሳ ብሔረሰቦች ፣ ለሴቶች እንዲሁም ለግለሰቦች ዕድል ለመስጠት ጥረት እንደሚደረግ ፣ የሁሉም ሀሳብ ይሰማ ከተባለ ግን ውይይቱ ከሚገባው በላይ እንደሚራዘም ገልጸው ኅዳር 1 ቀን 1987 ዓ.ም በተካሄደው ውይይት ላይ እንኳን ለክልል 13 ተወካዮች ከ2 ጊዜ በላይ ዕድል መስጠቱን አስታውቀው ከዚህ አንፃር የአንድ ግለሰብ ዕድል አለማግኘት ማለት የአናሳ ብሔረሰቦች ዕድል አለማግኘት ማለት እንዳልሆነ አስገንዝበዋል ፡፡

ከዚያም አቶ መሀሙድ ድሪር ከክልል 5 አንቀጽ 8 በኢትዮጵያ ታሪክ ለመጀመሪያ ጊዜ ሕዝቦች የሉዓላዊ ሥልጣን ባለቤት መሆናቸውን የሚደነግግ እንደሆነ ፣ በመርህ ደረጃ የሥልጣን ምንጭ ሕዝቦች መሆናቸውን ፣ ይህም በሕዝቦች ዲሞክራሲያዊ ተሳትፎ አማካይነት የሚያረጋግጥና ተወካዮቻቸውንም በቀጥታ መምረጥ እንዳለባቸው መቀመጡ እንደሚደገፉ ገልጸው የአንቀጹ ቅርጽን

በተመለከተ ግን ንዑስ አንቀጽ 1 የነበረው ንዑስ አንቀጽ 2 እንዲሆን ንዑስ አንቀጽ 2 የነበረው ደግሞ ንዑስ አንቀጽ 1 ቢሆን የሚል ማሻሻያ ሀሳብ አቅርበዋል ::

ቀተሎም አቶ ታደሰ አለማየሁ ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል አንቀጽ 8 በተመለከተ በሰጡት አስተያየት በኢትዮጵያ ታሪክ ሉዓላዊ የነበሩ መንግሥታት እንጂ ሕዝቦች እንዳልነበሩ ፣ በዚህም ሕዝቦች መገላታታቸውን ፣ ወደፊት በሚገነባው ዲሞክራሲያዊ ሥርዓት ግን ሕዝቦች ሉዓላዊ ሥልጣን ያላቸው መሆኑን በመግለጽ መቀመጡን ጠቁመው የአዲሱ ሕገ መንግሥት ተልዕኮ አገሪቱን ከግለሰቦችና ከፖለቲካ ኃይል አምባገነንነት መከላከልና ሕዝቡን ወደ ሕዝባዊ ሥልጣን ማሸጋገር በመሆኑ ሕዝቡ መሪዎችን ዲሞክራሲያዊ በመሆን መንገድ የመሻር ወይም የመሾም ምሉዕ ሥልጣን እንዳለው መቀመጡ አግባብ መሆኑን ፣ ለዘመናት ትግል የተካሄደውም በአንቀጹ የተቀመጡትን ጉዳዮች ዕውን ለማድረግ መሆኑን አስረድተው አቀማመጡን በተመለከተም በረቂቁ ባለው መልኩ ቢሆን እንደሚሻል ገልጸዋል ::

አክለውም ወ/ሮ መሠረት ተሾመ ከክልል 14 ሉዓላዊነትን የማይገድብ ፣ የማይጠየቅ የመንግሥት የመጨረሻው ሥልጣን ማለት እንደሆነ በሰጡት አስተያየት ሉዓላዊነት በቅድመ ደርግ በነገሥታት እጅ የነበረውና ነገሥታትም ፈላጭ ቆራጭ በመሆን ከሕዝቡ ይልቅ የእነርሱ ድምፅ ተሰሚ እንደነበርና ሕግ የማውጣት ሆነ የመጨረሻው ፍርድ የመስጠት ሥልጣን እንደነበራቸው አስታውሰው ደርግም ይህንኑ ያልተገደበ ሥልጣን ለፋሽሽታዊ ድርጊት ሲጠቀምበት መቆየቱን አመልክተዋል ::

አያይዘውም አንቀጹ ሕዝቦች ለዘመናት ያጡትን የሥልጣን ባለቤትነት የሚያጎናጽፍ ፣ ማንኛውም ሥልጣን ከሕዝቦች በታች እንጂ በላይ አለመሆኑን የሚገልጽና የሥልጣን ምንጭ ሕዝብ መሆኑን የሚያረጋግጥ ስለሆነ ባለው መልኩ ቢቀመጥ ትክክለኛ መስሎ እንደሚታያቸው ገልጸዋል ::

በሌላ በኩል አቶ ዳንኤል በላይነህ ከክልል 14 በሰጡት አስተያየት የሕዝቦች ሉዓላዊነት የሚረጋገጠው ሰብአዊ መብታቸው በተግባር ሲተረጎም መሆኑን ፣ በሕገ መንግሥት ደረጃ ባለፉት ሥርዓቶች መቀመጡን ግን በተግባር አለመተርጎሙን ገልጸው በሽግግር ወቅት ቻርተርም የመሰብሰብ ፣ ሰላማዊ ሰልፍ የማድረግ መብትና የፖለቲካ ድርጅቶች ሀሳባቸውን በነፃ የማንፀባረቅ መብት እንዳላቸው ፣ በአጠቃላይ የሕዝቦች ሉዓላዊነት በግልጽ መስፈሩን ፣ ተግባራዊነቱ ሲታይ ግን የፖለቲካ ድርጅቶ አላማቸውንና ፕሮግራማቸውን ማስተዋወቅ አለመቻላቸውን ጠቅሰዋል ::

አክለውም በሽግግሩ ወቅት የሕዝብ ሉዓላዊነት አለመጠበቁን ከሚያመለክቱት ክንውኖች መካከል ከሶማሊያ ጋር በተደረገው ጦርነት አገርን በመከላከል ረገድ ባለውለታ የሆኑት የኢትዮጵያ የጦር ሠራዊቶች አባላት ተበታትነው ለልመና



መዳረጋቸውን ፣ በመቶ ሺህ የሚቆጠሩ ሠራተኞች የመሥራት ዕድል ተነፍገው መሥራት ሲችሉ እቤት እንዲውሉ መደረጋቸውና በምትካቸው የውጭ ዜጎች እንዲተኩ መደረጉ እንደሚገኙበት ጠቁመው በበደኖና በአርባ ጉጉ የደረሰው የሰዎች እልቂትም ለአንድ ሳምንትና ለአስራ አምስት ቀናት የውይይት ርዕስ ብቻ መሆኑም ተጨማሪ የሕዝብ ሉዓላዊነት አለመከበሩን እንደሚያሳይ ጠቅሰዋል ::

አያይዘውም በሕገ መንግሥት ጉባኤው 85% አባላት ያለውና የሚፀድቀው ሕገ መንግሥትም የእርሱን ፍላጎት ሙሉ ለሙሉ እንደሚሟላ የሚገመተው ድርጅት የሽግግሩን ወቅት ቻርተር ከፈረሙት ድርጅቶች አንዱ መሆኑን አመልክተዋል ::

አክለውም የሚቀረፀው ሕገ መንግሥት የዜጎችን የመሥራት መብት የሚያረጋግጥ መሆን እንዳለበት ፣ የውጭ ዜጎች የያዟቸው የሥራ መደቦች ለቀው በአሁኑ ሰዓት ለሥራ አጥነት የተዳረጉት ዜጎች ችሎታ እየተገመተ የሥራ መደቦቹ ሊሰጧቸው እንደሚገባ አውስተው በአንቀጽ 8ም ሕዝብንና መንግሥትን የሚዳኝ ነፃ ፍርድ ቤት እንደሚቋቋም የሚገልጽ ዐረፍተ ነገር እንዲቀመጥ ጠይቀዋል ::

ከዚያም አቶ ሙሉጌታ ሃ/ሕይወት ከክልል 1 በሰጡት ማሳሰቢያ ከተጀመረ ጀምሮ ለጉባኤተኞች ሆነ ለጭቁኑ ሕዝብ ሳይሆን ጉዳዩ በቀጥታ ለሚመለከታቸው ወገኖች እንዲደርሱ ተብለው በሚደረጉ ንግግሮች ለሚነሱ አንዳንድ ጉዳዮች መልስ በመስጠት ጉባኤው ጊዜ እንዳያጠፋና አንዳንድ ማብራሪያ ለሚያስፈልጋቸው ጉዳዮች ብቻ ማብራሪያ እየተሰጠ ቢታለፍ እንደሚሻል ገልጸዋል ::

የጉባኤው ሊቀመንበር ይህንን ጉዳይ በተመለከተ በሰጡት መልስ አንድ ግለሰብ በውስጠ ደንቡ የተቀመጡትን ሥነ ሥርዓቶች ሳያጓድል የሚደርስበትን መደምደሚያ ለማዳበር ይረዳኛል ብሎ ካመነ የፈለገውን ሀሳብና ክርክር ማቅረብ እንደሚችል ገልጸው የተሰጠውን ማሳሰቢያ መልስ የሚሰጡ ግለሰቦች ሊጠቀሙበት እንደሚችሉ አመልክተዋል ::

አቶ መኩሪያ ታፈሰ ከክልል 14 ያለፉት ሕገ መንግሥታት ተግባራዊ ሊሆኑ ያልቻሉት የሉዓላዊ ሥልጣን ባለቤትና ምንጭ በትክክል ባለማስቀመጣቸው መሆኑን በማስመልከት በሰጡት አስተያየት አንቀጹ አዲሱን ሕገ መንግሥት ካለፉት ሕገ መንግሥታት በሚገባ ከሚለዩት አንቀጾች አንዱ እንደሆነ ጠቅሰዋል ::

አያይዘውም የሚመሠረተው መንግሥት የዜጎችን መብት የሚያስከብር መሆኑን ለማመልከት በመጀመሪያው ንዑስ አንቀጽ " ... ለሕግ ተገዢ የሆነ ፣ የብሔር / ብሔረሰቦችን ፣ የዜጎችንና የግለሰቦችን መብት አክባሪ ፌዴራላዊ መንግሥት በዚህ ሕገ መንግሥት መሠረት ይቋቋማል :: " የሚል እንዲታከልበት የማሻሻያ ሀሳብ አቅርበዋል ::

ቀጥሎም አቶ ዘለሌ ፀጋሥላሴ ከክልል 14 በሰጡት አስተያየት ከታሪክ መረዳት እንደሚቻለው ሕዝቦች ራሳቸውን ሲያስተዳድሩ የሥልጣን ባለቤትነታቸው ወይም ሉዓላዊነታቸው በኃይል ሊነጠቅ ስለሚችል ይህን ለመከላከል በመጀመሪያው ንዑስ አንቀጽ ላይ "... ሕዝባዊ ልዕልና ወይም የሕዝብ ሥልጣን በኃይል ወይም በሕገወጥ መንገድ ሊነጠቅ አይችልም ፡፡ " የሚል ቢጨመርበት የተሻለ ይሆናል የሚል ሀሳብ አቅርበዋል ፡፡

ከዚያም ዶ/ር አብዱልመጂድ ሁሴን ከክልል 5 ቀደም ሲል የተነሱት አንዳንድ ነጥቦችን በተመለከተ በሰጡት አስተያየት የኢትዮጵያ ጦር ከሶማሊያ ጋር ተዋግቷል ሲባል ሶማሌዎች በኢትዮጵያ የሚገኙ መሆናቸውና የተቀረውን ሕዝብ ለመግዛት ጦርነት ያላነሱ በመሆናቸው አነጋገሩ ሊታረም እንደሚገባ አሳስበው ተመሳሳይ አስተሳሰብ ባላቸው ጥቂት ክፍሎች በሶማሌዎች ላይ በአንዳንድ መሥሪያ ቤቶች ሳይቀር ልዩነቶች እንደሚደረግባቸውና በዚህ ረገድም ጥቆማዎች ለድርጅታቸው እንደሚደርሱ ገልጸው በአንዳንድ ቦታዎችም አገራችሁን አጥፍታችሁ የኛንም ልታጠፉ መጣችሁ የሚሉ እንዳልጠፉ ፣ ኢትዮጵያውያን ሶማሌዎች የፈለጉትን ለማድረግ ከመቼውም ጊዜ ይበልጥ ነፃነት ያላቸው በመሆኑ እንደ ባዕድ በመቁጠር መገፋፋት አይበጅም ሲሉ አስጠንቅቀዋል ፡፡

አክለውም ሶማሌዎች የመረጡትና የመጡት ከሌሎች ዲሞክራት ወንድሞቻቸውና እህቶቻቸው ጋር በመሆን አዲስቷን ኢትዮጵያን ለመገንባት እንደሆነና የድሮውን ሥርዓት ለመመለስ የሚያልሙ ካሉም ሕልማቸው ዕውን እንዳይሆን እንደሚታገሏቸው ጨምረው አስገንዝበዋል ፡፡

አያይዘውም የቀድሞ ጦር አባላትን በተመለከተ ለተነሳው ጉዳይም የሽግግሩ መንግሥት የቀድሞ መንግሥት ወታደሮችን ለማቋቋምና አዲስ ሕይወት እንዲጀምሩ ለማድርግ የትኛውም መንግሥት ሊያደርገው ከሚችለው በላይ ጥረት ማድረጉንና በዕርዳታም ሆነ በብድር የተገኘ በብዙ ሚሊዮን የሚቆጠር ገንዘብ ለዚሁ ተግባር መዋሉን ፣ ከዚህ አንፃር የሽግግር መንግሥቱ ከአንዳንድ የፖለቲካ ቡድኖች ይበልጥ አስተዋፅኦ መድረጉን ገልጸው የአንድ ሰው የቃላት አጠቃቀም የራሱ የግለሰቡን አስተሳሰብ እንደሚያንፀባርቅ፣ የጦር ሠራዊት ሲባል ቃሉ ራሱ አጥቂነትን እንደሚያመለክት ፣ በአሁኑ ጊዜ አገሪቱ ለጦርነት እንደማትዘጋጅና ስያሜውም እንደማትጠቀምበት ፣ ነፃነትን የሚገፍ ኃይል ከመጣም በመከላከያ ኃይል መታገል እንደሚቻል አስታውቀዋል ፡፡



ቀጥለውም በቻርተሩ የተሰጠው መብት የፖለቲካ ድርጅቶች እንዳይጠቀሙ ተደርጓል የተባለውን በተመለከተም ይህ ቢሆን ኖሮ እንደ ዘመነ ደርግ ይህ የጉባኤ አዳራሽ በአንድ የፖለቲካ ፓርቲ አባላት ብቻ በተሞላ ነበር ብለዋል ፡፡

በተጨማሪም በበደኖና በአርባ ጉጉ የተፈጸመው ጥፋት ሁሉንም ያሳዘና እንደነበር አስታውሰው የጥቃቱ ሰለባዎች ከአማራ ፣ ከኦሮሞ ፣ ከጉራጌና ከሶማሌ ብሔረሰቦች ሆኖ ሳለ በአንድ ብሔረሰብ ላይ ብቻ እንደተፈጸመ አድርጎ ማቅረቡ ተገቢ እንዳልሆነ ጠቁመው ድርጊቱም መታየት ያለበት ኢሰብአዊ ድርጊቶች በማንም ግለሰብ ፣ ብሔረሰብና ድርጅት መፈጸማቸው ተቀባይነት እንደማይኖረው እንጂ እሳት ከመጫር አንፃር መሆን እንደሌለበት ፣ ዲሞክራሲም ስኬት ሊኖረው እንደሚገባ አስገንዝበዋል ፡፡

በመጨረሻም ዶ/ር አብዱልመጂድ ሁሴን ቀደም ሲል በአንቀጽ 8 ንዑስ አንቀጽ 1 ፣ ንዑስ አንቀጽ 2 ፣ ንዑስ አንቀጽ 2 ደግሞ ንዑስ አንቀጽ 1 እንዲሆን የቀረበው ሀሳብ ተገቢ አለመሆኑንና ባለበት መልክ ቢቀመጥ የተሻለ መሆኑን ገልጸዋል ፡፡

ቀጥሎም አቶ ኃይሉ ገመዳ ከክልል 4 አንቀጹ ሕዝብ የሥልጣን ምንጭ መሆኑን በማያሻማ መልኩ የሚገልጽ በመሆኑ እንዳለ እንዲቀመጥ አመልክተው በየወቅቱ በአገሪቱ ላይ የሚነሱትን ወራሪዎችን ለመመከት በራሳቸው ስንቅና ትጥቅ አኩሪ መስዋዕትነትን የከፈሉ ጀግኖችን በአክብሮትና በአድናቆት እንደሚመለከቷቸው ፣ በአንፃሩ ግን በውስጥ ግጭቶችን ለመሳፍንቶች የግዛት ማስፋፊያ መሣሪያ ሆነው የብዙ ብሔር / ብሔረሰቦችን ሕልውና የተዳፈሩትን እንደ ጀግና እንደማያዩዋቸው እና ተግባራቸውም መጥፎ መሆኑን አስገንዝበዋል ፡፡

አያይዘውም አንዳንድ የጉባኤ አባላት ያለፉት ሥርዓቶች ፀረ- ዲሞክራሲ እንደነበሩ ከተናገሩ አገሪቱ ስትከተለው የነበረው የጦርነት መርሆ ስለተለወጠ የአፈና መዋቅራቱን መፍረስም መቀበል እንደነበረባቸው አስረድተው ፣ በተጨማሪም እነዚህ ለአፈና ተቋማቱ መፍረስ የሚቆረቆሩ ኃይሎች ለሕዝብ የሚያስቡ ከሆነ ለምን ሕዝባዊ የመከላከያ ኃይል እንገንባ አላሉም ሲሉ ጠይቀዋል ፡፡

አክለውም በበደኖና በአርባጉጉ የተገደሉት ሰዎች ለተወሰነ ጊዜ ብቻ የመወያያ ርዕስ ሆነው ቆይተዋል የተባለውን በተመለከተም እነዚህንም ሆነ በጊዜው የሚያልፉትን ሰማዕታት እንዘክር ካልን ዓመቱን በሙሉ ብሔራዊ የበዓላት ቀን ሆኖ ሊያልቅ ስለሚችል ሁሉንም ማክበር አዳጋች እንደሆነ ፣ ይህ ማለት ግን ያንን ፋሽሽታዊና አረመኔያዊ ድርጊት መደገፍ ወይም አሳንሶ መመልከት እንዳልሆነና ይልቁንም ድርጊቱ በሐዘን እያስታወሱ ደግሞ ዳግመኛ እንዳይፈጸም በአጠቃላይ የሕዝቦች ሉዓላዊነት እንዲከበር የበኩላችንን አስተዋፅኦ እናድርግ ሲሉ አሳስበዋል ፡፡

ከዚያም አቶ ዓለምሰገድ ገ/አምላክ ከክልል 1 በበኩላቸው የቀረቡትን የማሻሻያ ሀሳቦችና የተነሱትን አንዳንድ ነጥቦችን በተመለከተ በሰጡት አስተያየት የአንቀጽ 8 ንዑስ አንቀጾች በረቂቁ ላይ በተቀመጠው መልኩ ቢሆን እንደሚሻል አመልክተው አቶ መኩሪያ ታፈሰና አቶ ዘለሌ ፀጋሥላሴ ከክልል 14 ያቀረቧቸው የማሻሻያ ሀሳቦችም በአንቀጽ 9 ንዑስ አንቀጽ 2 እና 3 ላይ የተመለሱ በመሆናቸው እጠቃላይ አንቀጹ መመለስ ያለበትን የሉዓላዊነት ሥልጣን ባለቤት ማን ነው ? በምን ይገለጻል ? እንዴት ይገለጻል ? የሚሉትን መሠረታዊ ጥያቄዎችን የመለሰ በመሆኑ ማሻሻያ እንደማያስፈልገው አስረድተዋል ::

አክለውም ለወደፊቱ የሕዝብ ሉዓላዊነትን ለማረጋገጥ ያለፈውን በደልን መርምሮ መንግሥትና ሕዝብን የሚዳኝ ነፃ ፍድር ቤት ይቋቋማል የሚለውን የማሻሻያ ሀሳብን በተመለከተ መነሻው ትክክል እንዳልሆነና አስፈላጊነቱም እንደማይታያቸው ገልጸው መነሻው የአገር ነፃነትን ሲያስከብር የቆየው ሠራዊት ተበትኗል የሚል ሲሆን ሠራዊቱ ግን በኢትዮጵያውያን ዘንድ የሚታወቀው ከተጠ ቀሰው ሚና ይልቅ በመብት አፋኝነቱ በተለይም ለገዢ መደቦች የአፈና መሣሪያ መሆኑን ሌሎች ብሔር ብሔረሰቦች ብቻ ሳይሆን የአማራ ጭቁን ሕዝቦችም እንደሚያውቁት አመልክተዋል ::

ሠራዊቱ በጎጃም ፣ በሰሜን ሸዋ ፣ በትግራይ ፣ በኢትዮጵያ ሶማሊና በኦሮሞዎች ላይ ታሪክ የማይረሳው ግፍ በመፈጸሙ ምክንያት በጭቁኖች ትግል ሲደመሰስ ያዘኑትና ዛሬም የሚጮኹት የኢትዮጵያ ጭቁን ሕዝቦች ሳይሆኑ የነበረው ሥርዓት ተጠቃሚዎች ፣ ነፍጠኞችና ትምክህተኞች መሆናቸውን አስረድተዋል ::

በተጨማሪም ቀድሞውኑ ለዕለት ጉርሳቸው ሲሉ የሠራዊቱ አባል የነበሩ ወገኖች መዋቅሩ ሲፈርስ እንዳልተበታተኑና እንዳልተጣሉ ገልጸው ለዚህ ተግባር ስኬታማነት የሽግግር መንግሥቱ በመጀመሪያ አዋጅ ማውጣቱንና አዋጁን ተግባራዊ ማድረጉን ፣ አብዛኞዎቹም ወደ የቀያቸው ተመልሰው የቀድሞ ሥራቸውን በመሥራት አዲስ ሕይወት መጀመራቸውን ጠቅሰው ከሞፈር ይልቅ ቃታ መሳብን ሠርቶ ከማደር ይልቅ ሌብነትን የመረጡ እንዲሁም ለአንዳንድ ኃይሎች ቤንዚን ማርከፍከፊያ ልንሆን እንችላለን በሚል የኢትዮጵያ ሕዝብና የሽግግር መንግሥቱ በመውሰድ ላይ ያለውን እርምጃ እንዲዳፈን የሚፈልጉ ከቁጥር የማይገቡ መኖራቸውም ሊታወቅ እንደሚገባ አስገንዝበዋል ::

አስከትለውም በበደኖና በአርባጉጉ ተፈጸመ የተባለውን ግፍ በተመለከተም በበደኖ ግፍ መፈጸሙን ፣ በአርባጉጉም ድብቅ አላማ ባላቸው ሰዎች አማካይነት



ነዋሪውን የጎዳ ጥፋት መድረሱን ያም ሆኖ ሕዝቡ እርስ በርሱ ሊጨፋጨፍ አለመፈለጉን እንዳስመሰከረና በሁለቱም አካባቢዎች ለተፈጸሙት ድርጊቶች ሕዝቡ በጊዜው ፍርድ መስጠቱን ገልጸዋል ::

አክለውም በዚህ ጉባኤ አንድ ድርጅት 85 % ወንበር ስለመያዙና አንደንድ ድርጅቶች በቻርተሩ የተቀመጠውን መብት ተነፍገናቸው መንቀሳቀስ አልቻሉም የተባለውን በተመለከተም ድርጅቱ የተጠቀሰውን ያህል ወንበር የያዘው በመስኮት ገብቶ ሳይሆን መዋቅሩን እስከ ገጠር ዘርግቶ የሚንቀሳቀስ በመሆኑና በአጠቃላይ ከገጠር ከተማ ፣ ከከተማም አዲስ አበባን ፣ ከአዲስ አበባም ሒልተን ሆቴልንና ኢምባሲዎችን ብቻ ባለመምረጡ እንዲሁም ትናንት ከሕዝቦች ጋር በመሆን ታሪክ የማይረሳው መስዋዕትነት በመክፈሉ በሕዝብ ተመርጦ እንደሆነ ፣ በጉባኤው ተካፋይ የሆኑ የቤንሻንጉል ፣ የሶማሌና የአፋር ወዘተ... ድርጅቶችም በአንድ ሆቴል ብቻ የሚንቀሳቀሱ ሳይሆኑ ከሕዝቦቻቸው ጋር የሚኖሩና የሚንቀሳቀሱ መሆናቸውን ገልጸው በአጠቃላይ ከሕዝብ ጋር መኖር የሚችል የሕዝብን ድጋፍ ያገኛል የሚለው ሐቅ መታወቅ እንዳለበት አብራርተዋል ::

በመጨረሻም የሕዝብ ውክልናን ለማግኘት ሕዝብ መሆንና በሕዝብ ድጋፍ ማግኘት የሚያስችል አላማና ታሪክ መያዝን እንደሚጠይቅ አለያም ቢሞኙትም እንደማይገኝ ሊታወቅ እንደሚገባ አስገንዝበዋል ::

ቀጥሎም አቶ ዳንኤል በላይነህ ከክልል 14 ቀደም ሲል በንግግራቸው ሶማሌ ብለው የተናገሩት የሶማሊያ መንግሥትን ለማመልከት እንደነበር ፣ እዚህ የተሰበሰበው ሁሉ ኢትዮጵያዊ ነው በሚል እምነት እንደሆነ ጠቅሰው ዶ/ር አብዱልመጂድ ሁሴን ከክልል 5 ግን በንግግራቸው የቃሉን ትርጉም አዛብተው በመጥቀሳቸው ቅሬታ እንደተሰማቸው ገልጸዋል :: ሶማሌ ሲባል ኢትዮጵያዊ ሊሆን ስለሚችል ለይቶ መናገር እንደሚያስፈልግ የጉባኤው ሊቀመንበር አሳስበዋል ::

ከዚያም አቶ ዩሱፍ መሐመድ ከክልል 2 አንቀጹ በረቂቁ ባለው መልኩ መቀመጡን ደግፈው ሌሎች የተነሱትን ነጥቦች በተመለከተ በሰጡት አስተያየት ባለፉት ሥርዓቶች የሕዝብ ተወካይ ለመሆን ሀብትና ንብረት ይጠየቅ እንደነበረ ፣ ዛሬ ግን ሕዝቡ ያመነባቸውን የብሔር / ብሔሰቦች ተወካዮች ባህላዊ ልብሶቻቸውን ለብሰው በጉባኤው ላይ መሳተፋቸው በራሱ የሕዝቦችን ሉዓላዊነት የተከበረ መሆኑን እንደሚያመለክት ገልጸዋል ::

አያይዘውም በክልሎች ደረጃም የብሔር / ብሔረሰቦች መብት እየተከበረ መሆኑን ፣ ለምሳሌ በአፋር ክልል ቀደም ሲል ተምሮ እንዳልተማረ ተቆጥሮ የሥራ ዕድል ተነፍጎት የነበረው አሁን በመንግሥት መሥሪያ ቤቶች ተቀጥሮ ክልሉን

J000038



በማገልገል ላይ እንደሚገኝ ጠቁመው ዘበኛ በነበረበት መሥሪያ ቤት የመምሪያ ኃላፊ ሆኖ የሚሠራ እንዳለም ገልጸው አጠቃላይ የለውጡ ሂደትን በተመለከተ ኢትዮጵያ ማለት አዲስ አበባ ብቻ ባለመሆኑ ወጣ ብሎ መመልከቱ ለግንዛቤ እንደሚጠቅም አስረድተዋል ::

አክለውም አንዳንድ የጉባኤው አባላት ያለፉትን መጥፎ ድርጊቶች ጥሩ እያስመሰሉ ማቅረባቸው ትክክል ያለመሆኑንና መጥፎ ድርጊቶች የሚነሱት ለበቀል ሳይሆን ወደፊት እንዳይደገሙ ትምህርት ለመስጠት እንደሆነ ፣ ይህ ባይሆን ኖሮ በትግራይ ሕዝብ ላይ የቦንብ ናዳ ያወረደው ለገሠ አስፋው ዛሬ በሕይወት ባልኖረ ነበር ሲሉ አመልክተዋል ::

ቀጥሎም የጉባኤው ዋና ፀሐፊ አቶ አዲሱ ለገሠ በተነሱት አንዳንድ ነጥቦች ላይ በሰጡት አስተያየት ስለየቀድሞ ጦር ጀግንነት የተነሳውን በተመለከተ ያልነበረ ብዙ ሊያወራ ቢችልም በቦታው የነበሩ ሰዎች የሰጡት መልስ በቂ መሆኑን ገልጸዋል ::

አያይዘውም አንዳንድ ካለፈው ሥርዓት ማዕድ ወይም ከትርፍራፊው የተቋደሱ የጉባኤው አባላት የበሉበት ወጪት እንዳይሰበር ለኢሠፓ ባለሥልጣኖችና ለወታደሩ ሲቆረቆሩ በቆዩበት አንደበታቸው ዛሬ ደግሞ ለሠራተኛው ተቆርቋሪ መስለው መቅረባቸው የሚያስገርም መሆኑን ጠቁመው ጉባኤው ግን እንዲህ የሚሳሱለትን ወጪት እንደሚሰብር ፣ በተለይ አንድ አባል "እኔ አሻንጉሊት አይደለሁም ::" በማለት ሌሎች የሕዝብ ተወካዮች እንደ አሻንጉሊት መቁጠራቸው ለሕዝቦች ሉዓላዊነት ያላቸውን ዝቅተኛ ግምት እንደሚያሳይ እንዲሁም የጉባኤው 85% ወንበር በአንድ ድርጅት መያዙን በተደጋጋሚ ሲናገሩ ድርጅቱ በምን ያህል ሕዝብ ተመርጦ እንደመጣ ለተናጋሪዎቹ ጠፍቷቸው ሳይሆን ጉዳዩ ሕዝብን ከመናቅ የመነጨ እንደሆነና ሉዓላዊነትን መናቅ በጉባኤው ውስጥ በአንዳንድ ተናጋሪዎች አስተሳሰብ እየተገለጸ መሆኑን አመልክተዋል ::

በተጨማሪም እነዚህ ወገኖች የሚፈልጉት የሕዝብን ሉዓላዊነት ማስጠበቅ ሳይሆን የኢሠፓዎች የበላይነትና የቀድሞ ወታደሮች በሕዝብ ላይ የሚያደርሱትን ጭፍጨፋ መቀጠል እንደሆነ ፣ የእነዚህ ወገኖች አካሄድ የወከላቸውን ሕዝብ መብት የማያስጠብቅ እና የመረጣቸው ሕዝብ ሳይቀር የሚታዘባቸው መሆኑ ረጋ ብለው እንዲያስቡበት አሳስበዋል ::

ከዚያም ለአንቀጹ ቀርበው ከነበሩት ማሻሻያዎች ሁለቱን ሀሳብ አቅራቢዎች በማንሳታቸው በተቀሩት ሁለት ሀሳቦች ላይ በየተራ ድምፅ ተሰጥቷል ::

J000039



በዚህም መሠረት በአቶ መኩሪያ ታፈሰ ከክልል 14 የቀረበውና በአንቀጽ 8 ንዑስ አንቀጽ 1 ላይ "... ለሕግ ተገዢ የሆነ ፣ የብሔር / ብሔረሰቦችን ፣ የዜጎችንና የግለሰቦችን መብትና ነፃነት አክባሪ ፌዴራላዊ ዲሞክራሲያዊ መንግሥት በዚህ ሕገ መንግሥት መሠረት ይቋቋማል ::" የሚል እንዲታከልበት የቀረበው ማሻሻያ ለድምፅ ቀርቦ ድጋፍ 2 ፣ ተቃውሞ 518 ፣ ድምፀ ተአቅቦ 4 በመመዝገቡ መሻሻያው ውድቅ ሆኗል ::

በአቶ ዘሌለ ፀጋሥላሴ ከክልል 14 በአንቀጽ 8 ንዑስ አንቀጽ 1 ላይ "...ሕዝባዊ ልዕልና ወይም የሕዝብ ሥልጣን በኃይል ወይም በሕገ ወጥ መንገድ ሊነጠቅ አይችልም ::" የሚል ዐረፍተ ነገር እንዲጨመርበት ያቀረቡትን ማሻሻያ ሀሳብ ለድምፅ ቀርቦ ድጋፍ 3 ፣ ተቃውሞ 518 ፣ ድምፀ ተአቅቦ 4 በመመዝገቡ ማሻሻያው ተቀባይነት ሳያገኝ ቀርቷል ::

በመጨረሻም አንቀጽ 8 በረቂቅ ሕገ መንግሥቱ ላይ ባለው መልክ ያለ ምንም ማሻሻያ ለድምፅ ቀርቦ ከ5 ድምፀ ተአቅቦ በስተቀር በተቀሩት የጉባኤው አባላት ተደግፎ ፀድቋል ::

ከዚያም ውይይቱ በአንቀጽ 9 ላይ ቀጥሎ ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ ከክልል 14 በሰጡት አስተያየት አንቀጽ 9 ንዑስ አንቀጽ 4 ኢትዮጵያ ያፀደቀቻቸው ዓለም አቀፍ ስምምነቶች የሀገሪቱ የሕግ አካል መሆናቸውን እንደሚገልጽ ጠቅሰው ኢትዮጵያ ካፀደቀቻቸው ሕጎች አንዱ የተባበሩት መንግሥታት ድርጅት የ1948 /እ.አ.አ/ የሰብአዊ መብት ድንጋጌ እንደሚገኝበት ሆኖም ድንጋጌዎቹ 75 % በአሪቱ በሥራ ላይ እንዳልዋሉ ገልጸው ለዚህም ምሳሌ ሲጠቅሱ ከድንጋጋዎቹ አንዱ ማንም ሰው ራሱ በፈጸመው ጥፋት ዳኛ ፊት ቀርቦ ካልተፈረደበት በስተቀር ጥፋተኛ ወይም ወንጀለኛ አለመሆኑን እንደሚደነግግና በዚሁ አንቀጽም ማንም ሰው የዚህ ድርጅት አባል ነበርክ ወይም የዚህ ድርጅት አባል አትሁን ተብሎ ሊወቀስ ወይም ሊወንጀል እንደማይችል የሚገልጽ መሆኑን አመልክተው ኢሠፓ በአንድ ወቅት የነበረ የፖለቲካ ድርጅት ሆኖ ሳለ ቀይ ሽብርን የተቃወሙና ለሰብአዊ መብት የታገሉ የድርጅቱ አባላት ጭምር እየተሰቃዩ መሆናቸውን ገልጸዋል ::

አክለውም ቀደም ሲል የተነሳውን የጦር ኃይል ጉዳይን በተመለከተም ጦር ኃይል ማለት በእንግሊዝኛው "Armed Forces" እንደሆነና ይህም አጥቃ ሲሉት የሚያጠቃ ተከላከል ሲሉት የሚከላከል ኃይል መሆኑን ስያሚውም በመላው ዓለም እየተሰራበት ያለ እንደሆነ አመልክተዋል ::

ዶ/ር አብዱልመጂድ ሁሴን ከክልል 5 ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ ቤቱን ወስኖ ወደለፈው ጉዳይ እየመለሱት በመሆኑ በርዕስ ጉዳዩ ላይ እንዲያተኩሩ ይደረግ

የሚል የሥነ ሥርዓት ጥያቄ ቀርቦ ሊቀመንበሩ ማንም የጉባኤው አባል በተያዘው አጀንዳ ላይ ሀሳቡን መስጠት እንደሚችል ገልጸው በዚሁ መሠረት ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ ወደ ርዕስ ጉዳዩ ተመልሰው በአንቀጽ 9 ላይ የሚጨመር ወይም የሚቀነስ ነገር አለ የሚሉ ከሆነ ይህንኑ እንዲያቀርቡ አሳስበዋል ።

ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ በበኩላቸው አነሳሳቸው ኢትዮጵያ የፈረመቻቸው ዓለምአቀፍ ስምምነቶች የአገሪቱ የሕግ አካል ይሆናሉ ተብሎ በመቀመጡ እና ከስምምነቶቹ አንዱ ደግሞ ሰብአዊ መብትን መጠበቅ ሆኖ ሳለ በሽግግር መንግሥቱ መጣሱንና ወደፊትም ይህ ሁኔታ የሚታረምበት መንገድ እንዲፈለግ ለመግለጽ እንደነበር ጠቅሰው በየቀኑ አቶ ዓለምሰገድ ገ/አምላክ አራት ጊዜ የመናገር ዕድል ሲያገኙ እሳቸው ግን ገና አንድ ዕድል ብቻ ማግኘታቸውን አስታውቀዋል ።

ቀጥሎም የጉባኤው ሊቀመንበር ዶ/ር ነጋሶ ጊዳዳ ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ ላቀረቡት አስተያየት በሰጡት ምላሽ በሳምንቱ ውስጥ ከአቶ ዓለምሰገድ ገ/አምላክ ይበልጥ የመናገር ዕድል ለሻለቃ አድማሴ ዘለቀ ተሰጥቷቸው እንደነበር አስታውቀው አሁን በዚህ ዓይነት የሚሄዱ ከሆነ ዕድሉ ሊነፈጋቸው እንደሚችል ፣ በአንቀጹ ውስጥ ይካተት ወይም ከአንቀጹ ይውጣ የሚሉት ነገር ካለ ሊያቀርቡ እንደሚችሉ ቢገልጹም ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ ግን በትናንትናው ዕለት የጉባኤው ውይይትም ሊቀመንበሩ ሲጨቁኗቸው መዋላቸውን ጉባኤው ግን ከእርሳቸው ጋር እንደሆነና የጉባኤውን ፍርድ ሰምተው ቤቱን እንደሚለቁ ገልጸው ጉባኤውን ጥለው መውጣታቸውን አመልክተዋል ።

ቀጥሎም አቶ አባይ ፀሐዬ ከክልል 1 አንድ ሰው ጉባኤውን ጥሎ ከመውጣቱ በፊት ምክንያቱን ለጉባኤውና ለሕዝቡ ግልጽ አድርጎ ጉባኤውም አስተያየት ሊሰጥበትና ሊወስን እንደሚገባው ገልጸው በማናቸውም መንገድ ቢጣራ እንደ እሳቸው የመሰለውን ሀሳብ በሰፋትና በተደጋጋሚ ለማራመድ ወይም ለመግለጽ ዕድል ያገኘ ባለመኖሩ እንዲወጡ ያደረጋቸው ምክንያት የዲሞክራሲያዊ መብታቸው ታፍኖ አለመሆኑን ግልጽ መደረግ እንዳለበት አስገንዝበው የጉባኤውን ውስጠ ደንብ ሲጥሱ ለምን ሥነ ሥርዓት ተባልኩ ማለት ሰበብ ፍለጋ እንደሚመስላቸው ገልጸዋል ።

ወ/ሮ አለማሽ ግርማይ ከክልል 1 የቀረበውን ሀሳብና አመራሩ የወሰደውን እርምጃ ትክክለኛነት በመደገፍ በሰጡት አስተያየት ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ ቤቱን ጥለው የወጡበት ምክንያት ለጉባኤውና ለሕዝቡ ያላቸውን ንቀት የሚያመለክት እንደሆነና ይህም ከኮሚቴዎች ምርጫ ጊዜ ጀምሮ የአርሶ አደሩ ተወካዮች በኮሚቴዎች እንዳይገቡ ካደረጓቸው ተደጋጋሚ ንግግሮች በግልጽ ይታይ እንደነበረ አመልክተዋል ።



ቀጥሎም አቶ መሐመድ ሼክ አህመድ ከደቡብ ኢትዮጵያ ክልል ግለሰቡ በሰሞኑ ንግግራቸው ሕዝቦችን ለመከፋፈል መሞከራቸውን አውስተው ቤቱ በጉዳዩ ላይ ውሳኔ እንዲሰጥበት ጠይቀዋል ።

ከዚያም የጉባኤው ሊቀመንበር የሻለቃ አድማሴ ዘለቀን ተመልሶ ወደ ጉባኤ አዳራሹ መግባት ለቤቱ ገልጸው ማንኛውም አባል በጉባኤው የመካፈልም ሆነ ያለመካፈል መብት እንዳለው ፣ ያለመካፈል የፈለገ ግን ጉባኤውን አክብሮ ምክንያቱን ገልጽ አድርጎ መውጣት እንጂ እንደፈለገው ወጥቶ መግባት እንደማይቻል አሳስበው ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ የወጡበት ምክንያት ለቤቱ እንዲገልጹ ጠይቀዋል ።

ሻለቃ አድማሴ ዘለቀም በበኩላቸው ወጥተው የተመለሱበት ጉባኤው ምክንያትህን እንድታስረዳ ጠርቶሀል ስለተባሉ እንደሆነ ጠቁመው እርሳቸው ለቤቱ ከፍተኛ ፍቅርና አክብሮት እንዳላቸው ፣ የግል ጋዜጦችና ሕዝቡ 85% በአንድ ድርጅት በተያዘ ቤት ውስጥ ምን ታደርጋለህ በማለት እንዲወጡ እንደጎተጎቷቸው እርሳቸው ግን እስከተቻለና ተናግሮ መታሰር እስከ ሌለ ድረስ አልወጣም ብለው እየታገሉ መሆናቸውን ገልጸዋል ።

አያይዘውም የጉባኤው ሊቀመንበር አመራር ግን የሚያስወጣቸው ሆኖ እንዳገኙትና ተፈጸመብኝ ካሏቸው በደሎች መካከልም ሲጠቅሱ ከዚህ ቀደም 3 ገጽ ፅሑፍ አቅርበው አንድ በአንድ ካልሆነ በቀር አይቻልም ብለው ከመለሱባቸው በኋላ አቀርባለሁ ይላሉ ሆኖም አያቀርቡም ብለው መናገራቸው ፣ ከዚህም በተጨማሪ ሌሎች ድምፅ ተአቅቦ ያደረጉበትን ምክንያት የመግለጽ ዕድል ሲሰጣቸው ለእርሳቸው ግን ቢቃል እንዳያቀርቡ ተከልክለው በጽሑፍ እንዲያመጡ መታዘዛቸውንና በጽሑፍ ቢያቀርቡም ለቤቱ መነበብ ሲገባው መደበቁን ፣ በሌላ ቀንም በማያውቁት ጉዳይ ላይ ድምፅ ላለመስጠት የማብራሪያ ጥያቄ ለመጠየቅ እጅ ቢያወጡም ዕድል እንደተነፈጋቸው ገልጸዋል ።

አክለውም አንድንድ ግለሰቦች " እንደእሳቸው የመናገር ዕድል ያገኘ የለም ፣ ዲሞክራሲ አለ ለምን የለም ይላሉ ። " ብለው ሲተቹ መስማታቸውን ጠቁመው እነዚህ ሰዎች ቤት የተመለሰላቸው ፣ መሬት ተቆርሶ የተሰጣቸው በአጠቃላይ ሁሉ ነገር መንግሥቱ ሰማያት የሆነላቸው ናቸው ብለው ዲሞክራሲ የለም የሚለው ሌላው ወገን እንደሆነና ከጉባኤው ተካፋዮች እንኳን ብዙ በሆዱ የሚያስለቅስ እንዳለ ጠቅሰዋል ።

አስከትለውም እርሳቸው የሚሟጉቱት ዘጠኝ ዓመት ላሰራቸውና ወንድማቸውን ለገደለባቸውና ቤት ንብረታቸውን ለወረሰባቸው ለኢሠፓ በመሆኑ የበሉበትን

J00042


ወጪት ለመጠበቅ አለመሆኑን ፣ ለኢሕአዴግም ከፕሬዚዳንት መለስ ዜናዊ እና ከአቶ ተፈራ ዋልዋ ቀጥሎ 3ኛ ሰው መሆናቸውን ጠቅሰው በመጨረሻም የሽግግር መንግሥቱን ሲቃወሙ ራሳቸውን መያዝ እንደሌለባቸው በጉባኤውም የመቀጠል ተስፋ እንዳላቸው አመልክተዋል ::

የጉባኤው ሊቀመንበር በበኩላቸው ማንም የጉባኤው አባል በእሳቸው ምክንያት ጉባኤውን ለቆ እንዲወጣ እንደማይፈልግና ትክክልም እንዳልሆነ ጠቁመው ሊቀመንበሩ በጉባኤው እስከ ተመረጠ ድረስ የአመራር ስህተት ወይም ችግር ቢፈጠር እንኳን አጀንዳ አስይዞ መወያየት እንደሚቻል ፣ በዕለቱም ጉባኤውንና ሕዝቡን አክብረው ወደ ርዕስ ጉዳዩ እንዲገቡና ለጊዜ ቁጠባ ንግግራቸውን እንዲያሳጥሩ መጠየቃቸው አግባብ እንደነበረ ገልጸዋል ::

ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ ላቀረቧቸው ክሶች በሰጡት መልስም የድምፀ ተአቅቦ ምክንያታቸውን በፅሑፍ ማቅረባቸውንና ይህም የጉባኤው ሪኮርድ ሆኖ እንዲቆይ ገልጸው ከዚያ ሌላ አንዳችም ዓይነት ፅሑፍ ለአመራር አካሉ አለማቅረባቸውን አስታውቀው ፣ በተጨማሪም አንድ ጉዳይ ለድምፅ እንዲቀርብ ከተወሰነ በኋላ ሥነ ሥርዓት በመሆኑ የጥያቄም ሆነ የሌላ ዕድል እንደማይሰጥ ፣ ይህም ለሻለቃ አድማሴ ዘለቀ ብቻ ሳይሆን ለሌሎች አባላትም እየተሠራበት ያለ ሕግ መሆኑን ገልጸው የመናገር ዕድል ስለተነፈጋቸውም ሆነ አመራሩ ያደረሰባቸውን በደል እና የተፈጠረውን ሁኔታ በተመለከተ ቤቱ እንዲወያይበት አሳስበዋል ::

በዚሁ መሠረት አቶ ኩማ ደመቅሳ ከክልል 4 ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ በጉባኤው ያገኙት ዕድል የመናገር ብቻ ሳይሆን የመሳደብና ሕዝብን የማንቋሸሽ ጭምር እንደሆነ ፣ ማንም ሰው የመናገር ዲሞክራሲያዊ መብት አለው ስለተባለ ብቻ ከሥነ ሥርዓት ውጭ መናገር እንደሌለበት ፣ ከዚህ አንፃር አመራሩ ለግለሰቡ የሰጠው መብት ከተገቢው በላይ መሆኑን አስታውቀዋል ::

አያይዘውም ከመነሻው ጀምሮ በቤቱ ውስጥ ሁለት ዓይነት አስተሳሰቦች እንደነበሩ ፣ ከእነዚህም አንዱ ሻለቃ አድማሴ ዘለቀና ከቤቱ ውጭም እርሳቸው ጉባኤውን ለቀው እንዲወጡ የሚጎተጉቷቸው የግል ጋዜጦችና ሌሎች ሰዎች የወከሉት የዱሮውን ሥርዓት የሚያወድሱ ፣ ያለፈውን ቁስል የሚነካካ እንዲሁም የሕዝብን ክብርና የበላይነት የሚያንቋሽሽ እንደሆነ ገልጸው በዕለቱ ከጉባኤው የወጡትም እሳቸው እንዳሉት የመናገር ዕድል ተነፍጓቸው ወይም ሌላ ጭቆና ተደርጎባቸው ሳይሆን ወክለውት የቀረቡት አስተሳሰብ ከመጀመሪያ ጀምሮ አንቀጽ በአንቀጽ እየተሸነፈ በመምጣቱ እንደሆነ ጠቅሰው በቤቱ ውስጥ የሕዝብን አስተሳሰብ ወክሎ የተገኘው ኃይል እያሸነፈ የመጣው የሌላውን መብት በመንካት ወይም በመሳደብ ሳይሆን ትክክለኛውን የሕዝቦች በደል በመግለጽ እንደሆነ አስረድተዋል ::

J00043


የጉባኤው ዋና ፀሐፊ በበኩላቸው መድረኩ የሚመራው በጉባኤው ሊቀመንበር ብቻ ሳይሆን በጋራ መሆኑንና አመራሩ የጉባኤውን ውስጠ ደንብ የማስከበር ኃላፊነት እንዳለበት ፣ በንፅፅር ከታየ የመብት ጥያቄ ማንሳት ያለበት በጉባኤው 85% ወንበር ይዟል የተባለው ኃይል እንደነበር አስረድተዋል ::

አያይዘውም ሻለቃ አድማሴ ያቀረቡት ባለ ሶስት መሥመር የተአቅቦ ምክንያት አስፈላጊ ሆኖ ከተገኘ ለጉባኤው ሊነበብ እንደሚችል ጠቁመው ጉዳዩን ግን ከዚህ ቀደም በቃል ተነስቶ መልስ የተሰጠበት እንደሆነ ፣ በጋዜጣ ወጣ የተባለውን ጉዳይ በተመለከተም በጋዜጦች የሚነበበውና ከዚህ ቤት በአንዳንድ ሰዎች የሚነገረው ልዩነት የለውም ሲሉ ተናግረዋል ::

በመጨረሻም በሚቀጥለው ቀን በጉዳዩ ላይ ጉባኤው ተጨማሪ ውይይት ለማካሄድ ተስማምቶ የዕለቱ ስብሰባ ከቀኑ በ5:50 ሰዓት ተጠናቋል ::

ኅዳር 3 ቀን 1987 ዓ.ም ከጧቱ 3:00 ሰዓት ጀምሮ በሕገ መንግሥት ጉባኤ አዳራሽ የቀጠለው የኢትዮጵያ ሕገ መንግሥት ጉባኤ የተመራው በጉባኤው ሊቀመንበር በዶ/ር ነጋሶ ጊዳዳ ሲሆን በቅድሚያ የጉባኤው ዋና ፀሐፊ አቶ አዲሱ ለገሠ በዕለቱ የተገኙት የጉባኤ አባላት ብዛት 520 በመሆኑ ጉባኤውን መጀመር እንደሚቻል ገልጸዋል ::

ከዚያም የጉባኤው ሊቀመንበር ዶ/ር ነጋሶ ጊዳዳ ጉባኤው የሚነጋገርበት አጀንዳ

1. ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ ጉባኤውን ረግጠው ስለመውጣት ተጀምሮ የነበረውን ውይይት መቀጠል ፣
2. የጉባኤውን ቃለጉባኤ ቁጥር 6 እና 7 መርምሮ ማፅደቅ ፣
3. በረቂቅ ሕገ መንግሥቱ መወያየቱን መቀጠል ፣

የሚሉ እንደሆነ ገልጸው በመጀመሪያው አጀንዳ ላይ የጉባኤው ምክትል ፀሐፊ ማብራሪያ እንዲሰጡ ጋብዘዋል ::

በዚህም መሠረት የጉባኤው ምክትል ፀሐፊ አቶ አባተ ኪሾ ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ ጉባኤውን ረግጠው ከወጡ በኋላ ያለ ጉባኤው ጥሪ በራሳቸው ፈቃድ እንደገና ተመልሰው የጉባኤውን አመራር በተለይም ሊቀመንበሩ የመናገር መብትን ስለከለከሉኝ ነው የወጣሁት የሚል አቤቱታ በማቅረባቸው ቤቱ በረቂቅ ሕገ መንግሥቱ ላይ ሲያደርግ የነበረውን ውይይቱን አቋርጦ በዚሁ ጉዳይ ላይ ባለፈው ቀን ሲወያይ እንደነበርና በውይይቱ ወቅትም አቤቱታ አቅራቢው ጉባኤውን ረግጠው ከመውጣታቸው በፊት በደላቸውን ለጉባኤው ማስረዳት እንደነበረባቸው ፣ ይህም ባለማድረጋቸው ሥነ ሥርዓት ስለጣሱ ጉባኤው ጉዳዩን መርምሮ እና ያቀረቡትን አቤቱታ ተገቢ መሆኑን አለመሆኑን አይቶ ውሳኔ እንዲሰጥበት አሳስበዋል ::

በዚህም መሠረት አቶ ካሚል አህመድ ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል ከጉባኤው አባላት እንደ ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ የመናገር ዕድል ያገኘ አባል እንደሌለ ስለደርግ ኢሠፓና የቀድሞ ሠራዊት መብት በተደጋጋሚ ሲከራከሩ እንኳን በጉባኤው መድረክ እንደተስተናገዱ ፣ ተጠቃሹ ጉባኤውን ረግጠው የወጡት እሳቸው እንደሚሉት በጉባኤው አመራር አካላት የመናገር መብታቸው ስለታፈነ ሳይሆን አቋማቸው በእርሳቸው በኩል በግል ጋዜጦች እንዲፀባረቅላቸው በሚፈልጉ ቡድኖች ጉትጎታ እንደሆነ ፣ "ይህንንም ብዙ ሰዎች ከጉባኤው ውጣ ሲሉኝ አልወጣም ብዬ ነው ያልሁት :: " ብለው ራሳቸው ከተናገሩት ቃል ለመረዳት እንደሚቻል ፣ እንዲሁም እሳቸው እያንዳንዱ አርሶ አደር ከወከላቸው ጉባኤተኞች



እኩል መብትና ሥልጣን ስላላቸው በጉባኤው ውስጥ ደንብ መግዛት እንዳለባቸውና ከሌሎች አባላት ተለይተው እንደ ዕንቁ ሊታዩ እንደማይችሉ አብራርተዋል ::

ቀጥሎም አቶ አበበ ጎበና ከክልል 6 በሰጡት አስተያየት ባለፈው ጊዜ ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ የቀድሞ ሠራዊት የሚመለከቱ ጉዳዮች ባነሱ ጊዜ ጉዳዮቹ ከዕለቱ አጀንዳ ጋር የማይገናኙ በመሆናቸው የጉባኤው ሊቀመንበር እንዳቋረጧቸው ፣ ይህም የሊቀመንበሩ የሥራ ድርሻ እንደሆነ ፣ በስብሰባ ወቅት በተለይ በፓርላማ ስብሰባ ስብሰባውን ረግጦ መውጣት ቀርቶ ጫማ አውልቆ እስከ መደባደብ የተደረሰበት አጋጣሚ ስላለ ተጠቃሹ ጉባኤውን ረግጠው በመውጣታቸው ጥፋተኛ ቢሆኑም ይቅርታ ተደርጎላቸው ቢታለፉ እንደሚሻል አመልክተዋል ::

ከዚያም አቶ አብዱላሂ ኢብራሂም ከክልል 5 ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ በትምህርት ሆነ በፓርላማ በመሳተፍ ልምድ ያካበቱና የተከበሩ ግለሰብ እንደመሆናቸው መጠን ጉባኤውን እንዳላከበሩ ፣ ጉባኤው በረቂቅ ሕገ መንግሥቱ ውይይት ሲጀምርም የረቂቅ ሕገ መንግሥቱ አረቃቀቅ ኢ-ዲሞክራሲያዊ በመሆኑ አልቀበለውም ማለታቸውን ፣ ብዙን ጊዜ የጉባኤው አባላት ይደግፉኛል ቢሉም እሳቸው ጉባኤውን ረግጠው ሲወጡ አንድ አባል እንኳን እሳቸውን አለመከተሉ ሲታይ የሚደግፉቸው አለመኖሩን እንደሚያስገነዝብ ፣ የሳቸውን ያህል ሀሳቡን የመግለጽ ዕድል ያገኘ አባል እንደሌለ ገልጸው ይሁንና የዕድሚያቸውን መግፋት በመገንዘብ ከአባላቱና ከጉባኤው ሂደት ጋር ሊስማሙ እንደሚገባ አስረድተዋል ::

በሌላም በኩል ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ ለክልል 14 አቤቱታቸውን ያቀረቡት በጉባኤው አመራር ላይ ሆኖ ሳለ አመራሩ ራሱ የሚሰጣቸው የዳኝነት ብይን ተገቢነቱ እንደማይታያቸው ላቀረቡት ተቃውሞ የጉባኤው ዋና ፀሐፊ በሰጡት ምላሽ ጉባኤው ፍርድ ቤት እንዳልሆነ ፣ አመራር አካላቱም ዳኞች ሳይሆኑ በውስጠ ደንቡ መሠረት የጉባኤውን መድረክ የሚመሩ መሆናቸውን ጠቁመው ተጠቃሹ ግን የጉባኤው ሂደት እንቅፋት እንዲገጥመው በማድረግ የጉባኤውን ክብር እየነኩ በመሆናቸው በሳቸው ምክንያት የጉባኤው ሂደት መጓተት እንደሌለበት ገልጸዋል ::

ቀጥሎም አቶ ዓለምሰገድ ገ/አምላክ ከክልል 1 ጉባኤው ሥራውን ከጀመረ እስከ አሁን ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ የሚያራምዱት እየሞተ ያለውን የነፍጠኛ ሥርዓት አመለካከት በመሆኑና አመለካከቱም ሲሞት ማጣጣሩና መንፈራገጡ ስለማይቀር ጉባኤው ለሻለቃ አድማሴ ዘለቀ ከሚገባው በላይ ግምት ሳይሰጥ ጉዳዩ በድምፅ እንዲወሰን ሀሳብ አቅርበዋል ::

በሌላ በኩል አቶ ኢብራሂም ሱሌማን ከክልል 4 ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ ከማንም የጉባኤ አባል የበለጠ የመናገር ዕድል ለማግኘታቸው በዜና ማሰራጫዎች የሚተላለፈውን የጉባኤውን ሂደት የሚከታተለው የኢትዮጵያ ሕዝብ ምስክር እንደሆነ ፣ እያንዳንዱ የጉባኤ አባል እንደ ሕዝብ ተወካይነቱ እኩል መብት ስላለው እንደ ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ ያሉ አንዳንድ የክልል 14 ተወካዮች የፈለጉትን ብቻ በሕገ መንግሥቱ ይስፈር የሚሉ ከሆነ የማይቻል ስለሆነና የጉባኤው አላማም ኢትዮጵያን ለዲሞክራሲያዊ ሕገ መንግሥት ባለቤትነት ለማብቃት በመሆኑ ሕገ መንግሥቱን ሊያዳብሩ የሚችሉ ሀሳቦችን እንዲያቀርቡ አደራ ካሉ በኋላ ሻለቃ አድማሴ ዘለቀም የቃል ማስጠንቀቂያ ተሰጥቷቸው እንዲታለፉ ሀሳብ አቅርበዋል ::

ቀጥሉም አቶ ተመስገን ማሞ ከክልል 14 የክልል 14 ተወካዮችን በተመለከተ ከላይ የተሰነዘረው አስተያየት ከክልል 14 ተወካዮች መካከል በ15000 ያህል ሕዝብ የተመረጡ እንዳሉ ፣ ሻለቃ አድማሴ ዘለቀና አቶ ዳንኤል በላይነህ ሲመረጡ ያገኙት ድምፅ ቢደመር ግን 15000 ሊደርስ እንደማይችል ገልጸው ዲሞክራሲያዊ ሂደት በጉባኤው የሚያራምዱት የክልሉ ተወካዮች በርካታ መሆናቸው እንዲታወቅ አሳስበዋል ::

ከዚያም አቶ መኩሪያ ታፈስ ከክልል 14 የሻለቃ አድማሴ ዘለቀ በጉባኤው ሊቀመንበር ታፍኛለሁ የሚል አቤቱታ በማቅረባቸው ሊቀመንበሩ የጉባኤውን ውስጠ ደንብ መሠረት በማድረግ አመራራቸው እንዲታይላቸው ያቀረቡት ጉዳይ በመሆኑ በመጀመሪያ ሊቀመንበሩ አቤቱታ አቅራቢውን እንዳይናገሩ ማፈን አለማፈናቸውን ጉባኤው ማረጋገጥ እንዳለበት ከዚያም አቤቱታ አቅራቢው ከጉባኤው መወጣታቸው ጉባኤውን መርገጥ መሆኑን አለመሆኑን ሊወስን እንደሚገባ አመልክተዋል ::

ቀጥሉም አቶ አባይ ፀሐዬ ከክልል 1 ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ ምክንያታቸውን በቅድሚያ ሳይገልጹ የራሳቸውን አቋም በመያዝ ጉባኤውን ረግጠው መውጣታቸው የዲስፕሊን ስህተት መሆኑ አለመሆኑ መታየት እንዳለበት ፣ ከዚያም የጉባኤው ሊቀመንበር ተጠቃሹን ያፈኗቸው መሆኑን አለመሆኑን ጉባኤው ሊወስን እንደሚገባው ገልጸው ተጠቃሹ ታፍኛለሁ የሚለው የአቤቱታቸውን ለጉባኤው ሳያቀርቡ ጉባኤውን ረግጠው መውጣታቸው የዲስፕሊን ሥነ ሥርዓት መጣስ ስለሆነ ማስጠንቀቂያ ተሰጥቷቸው እንዲታለፉ የውሳኔ ሀሳብ አቅርበዋል ::

አቶ ዘለሌ ፀጋሥላሴ ከክልል 14 ተጠቃሹ ግለሰብ ጉባኤውን ረግጠው በመውጣታቸው የቅጣት ውሳኔ የማሳለፍ ሥልጣን የዲስፕሊን ኮሚቴ እንጂ ጉባኤው ሥልጣን እንደሌለው ላቀረቡት የተቃውሞ ሀሳብ የጉባኤው ሊቀመንበር አንድ





ደጋፊና አንድ ተቃዋሚ እንዲናገሩ ዕድል ስለሚሰጣቸው ተቃዋሚ ያኑ ሊቃወም እንደሚችል ምላሽ ሰጥተዋል ::

ከዚያም የውሳኔ ሀሳብ አቅራቢው አቶ አባይ ፀሐዬ ከክልል 1 የጉባኤው ሊቀመንበር በጠየቋቸው መሠረት ውሳኔ ሀሳቡ "በጉባኤው ውስጥ አንድ አባል መብቱን ተገፍፌያለሁ ፣ ተበድያለሁ በሚልበት ጊዜ ለጉባኤው አቅርቦ እንዲያይለት የማድረግ መብቱ በተጠበቀበት ፣ ሥርዓትም ተጥሷል ከተባለ እንደዚሁ በጉባኤ ውስጥ መብቱን ማስከበር የሚችልበት ሁኔታ ባለበት ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ ግን ይህን ሳያደርጉ አቤቱታቸውን እንዲገልጹ እየተጠየቁ ጉባኤውን ረግጠው መውጣታቸው አግባብነት የሌለውና የዲስፕሊን መጣስ በመሆኑ ማስጠንቀቂያ ይሰጣቸው :: " የሚል እንደሆነ ገልጸዋል ::

በዚህም መሠረት አቶ መኩሪያ ታፈስ ከክልል 14 የውሳኔ ሀሳቡን በመቃወም አንድ የጉባኤ አባል እንደ ሉዓላዊ ሕዝብ ተወካይነቱ የማይደፈር የሕዝብ መብት የተሸከመ በመሆኑ በጉባኤው ደስ የማይለው ሁኔታ ከገጠመው የጉባኤውን ሥነ ሥርዓት ደረጃዎችን ሳያልፍ ጉባኤውን ረግጦ ሊወጣ እንደሚችል ፣ አንድ የሀገር መሪም ስብሰባ ረግጦ ከወጣ እንደማይከሰስ ፣ ከዚህም አኳያ ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ የጉባኤውን ሥነ ሥርዓት እንዳልጣሱ አመልክተዋል ::

በሌላ በኩል የቀረበውን ውሳኔ ሀሳብን በመደገፍ አቶ ታደሰ አለማየሁ ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል ሕገ መንግሥቱን የማርቀቅና ማፅደቅ ሂደት የሀገር ጉዳይ በመሆኑ አባላት በሂደት ወቅት በውስጠ ደንቡ ሊተዳደሩ እንደሚገባ ፣ ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ ደንቡን በማፅደቁ በኩል ከፍተኛ ሚና የተጫወቱ ቢሆንም መልሰው በመጣሳቸው የቀረበውን የውሳኔ ሀሳብ ተገቢ እንደሆነ ገልጸው የሀገር መሪዎች ስብሰባ ረግጠው ሲወጡ አይከሰሱም በሚል ከላይ የተሰነዘረውን ሀሳብ ግን ስምተው እንደማያውቁ ጠቁመዋል ::

በመጨረሻም "አንድ አባል በጉባኤው ውስጥ አንድ አባል መብቴን ተገፍፌያለሁ ፣ ተበድያለሁ " በሚልበት ጊዜ ለጉባኤው አቅርቦ እንዲያይለት የማድረግ መብቱ በተጠበቀበት ፣ ሥርዓትም ተጥሷል ከተባለ እንደዚሁ በጉባኤ ውስጥ መብቱን ማስከበር የሚችልበት ሁኔታ ባለበት ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ ግን ይህን ሳያደርጉ አቤቱታቸውን እንዲገልጹ እየተጠየቁ ጉባኤውን ረግጠው መውጣታቸው አግባብነት የሌለውና የዲስፕሊን መጣስ በመሆኑ ማስጠንቀቂያ ይሰጣቸው :: " የሚለው የውሳኔ ሀሳብ ለድምፅ ቀርቦ ድጋፍ 512 ፣ ተቃውሞ 5 ድምፀ ተአቅቦ 5 ድምፅ በመመዝገቡ ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ ማስጠንቀቂያ እንዲሰጣቸው ተወስኗል ::

ቀጥሎም ቤቱ ውይይቱን የቀጠለው ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ የጉባኤው ሊቀመንበር የመናገር መብቴን አፍነውብኛል ብለው ባቀረቡት አቤቱታ ትክክል መሆን አለመሆኑን ላይ ሲሆን አቤቱታ አቅራቢው አቤቱታቸውን በድጋሚ እንዲያቀርቡ ተጋብዘዋል ::

በዚህም መሠረት አቤቱታ አቅራቢው በጉባኤው የሚከራከሩባቸው ጉዳዮች ብዙ ከመሆናቸው የተነሳ ሀሳባቸውን በፅሑፍ ለማቅረብ ጥያቄ አቅርበው ሳይፈቅዱላቸው እንደቀረ ፣ ቤቱ በስብሰባዊ መብቶች አንቀጾች በተወያየበት ወቅት ሌሎች የጉባኤ አባላት ሰስት ያህል ጊዜ ዕድል ሲሰጣቸው እሳቸው አንድ ዕድል እንኳን መከልከላቸውን ፣ እንዲሁም በቀረበው የውሳኔ ሀሳብ ቤቱ ድምፅ ከመስጠቱ በፊት ጥያቄ እንዳላቸው ጠይቀው እንዳልተፈቀደላቸው ፣ ድምፀ ተአቅቦ ያደረጉበትን ምክንያት ለመግለጽ ጠይቀውም ተአቅቦአቸውን በጽሑፍ እንዲያቀርቡ በስብሰባው ቢታዘዙት መሠረት ያቀረቡትም ለጉባኤው አባላት ሊቀርብ ሲገባው ሳይቀርብ መቅረቱን ገልፀዋል ::

አያይዘውም ጉባኤው ረግጠው ስለመውጣታቸው ሲገልጹም አንድ የፓርላማ አባል በደል ሲፈጸምበትና ሲከፋው ከስብሰባ ሊወጣ እንደሚችል ፣ ከዚህም አኳያ የጉባኤው ሊቀመንበር ለሌሎች አባላት ዕድል ሲሰጡ ለእርሳቸው ግን ዕድል በመከልከል ስላፈንዋቸው ከጉባኤው መውጣታቸውን ፣ ሲወጡም በመሬት ላይ እንጂ በሰው ላይ እንዳልተራመዱ ፣ ከወጡ በኋላ ወደ ጉባኤው የተመለሱትም ጉባኤው ቅሬታቸውን ሊያዳምጥ እንደጠራቸው ተገልጾላቸው እንደሆነ ፣ ይህንንም ጋዜጠኞች ሊመሰክሩላቸው እንደሚችሉ አመክልተዋል ::

አክለውም ከጉባኤው አባላት ብዙዎቹ ደጋፊዎቻቸው መሆናቸውን ስለሚያውቁ ለጉባኤው ከፍተኛ አክብሮት እንዳላቸው ገልጸው የጉባኤው ሊቀመንበር ሆነው በተቃዋሚዎቻቸው እያስተቿቸው የተሰጠው የማስጠንቀቂያ ውሳኔ ግን የሕግ ሚዛናዊነት እንደሌለው ፣ የእሳቸው ጉዳይ ላይ ውይይት መካሄድ የነበረበት ሌላ ገለልተኛ ሰው ጉባኤውን መምራት እንደነበረበት ጠቁመዋል ::

ከዚያም አቶ ዳንኤል በላይነህ ከክልል 14 ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ ጉባኤውን ረግጠው መውጣታቸው የሥነ ሥርዓት መጣስ ከሆነ የጉባኤው የዲስፕሊን ኮሚቴ ስላለ እሱ ጉዳያቸውን እንዲያይና እንዲወስን ፣ ከዚህ ውጭ ግን ለተጠቃሹ ደጋፊ በሌለበት ጉባኤው በተቃዋሚዎቻቸው እንዲተቹ ማድረጉ አግባብ እንዳልሆነ ገልጸዋል ::

በሌላ በኩል አቶ መሀሙድ ድሪር ከክልል 5 አንድ የጉባኤ አባል መጥፋት ፋይዳ ስለሌለው ብዙዎቹ የጉባኤው አባላት ሻለቃ አድማሴ ዘለቀን እንደሚወዱ ፣ በመሆኑም የጉባኤው አባላት ተጠቃሹ ሲሰሳቱ መሳሳታቸውን ሊገልጹ እንደሚችሉ



ሆኖም ግን ግለሰቡ የሚሳሳቱት ካለማወቅ ሳይሆን ሆን ብለው በመሆኑ የሥነ ሥርዓት እርምጃ ሊወሰድባቸው እንደሚገባ ገልጸው ከጉባኤው አባላት መካከል የሻለቃ አድማሴ ዘለቀን ያህል የመናገር ዕድል ያገኘ አለመኖሩን ፣ ይህም በቤና ማሰራጫዎች ከሚተላለፈው ፕሮግራም መረዳት እንደሚቻል አስረድተዋል ::

ቀጥሎም የጉባኤው ዋና ፀሐፊ ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ ለጉባኤው ሆነ ለጉባኤው አመራር አካላት ቢሮ የሚያቀርቡት ጽሑፍ ተቀባይነት እንዳላጣ ፣ የተአቅቦቸውን ምክንያት በመግለጽ ያቀረቡት ጽሑፍ በሰነድነት ተይዞላቸው በጉባኤው ጽሕፈት ቤት ከመቀመጥ ውጭ ለጉባኤው እንደገና ቀርቦ ውይይት ሊደረግበት እንደማይችል ይህም የተለመደ አሠራር እንደሆነ ፣ ተጠቃሹ እንዳይናገሩ በጉባኤው አመራር አካላት አንድም ጊዜ እንዳልታፈኑ ፣ ጉባኤውን ረግጠው ከወጡ በኋላ ለአመራር አካላት ባቀረቡት ጥያቄ መሠረት ተፈቅዶላቸው እንጂ በአመራር አካላቱ ልመና እንዳልሆነ አብራርተዋል ::

በመጨረሻም ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ ያቀረቡት ስሞታ ትክክል ነው መድረኩ አፍኗቸዋል የሚልና መድረኩ ብዙ ዕድል ስለሰጣቸው ያቀረቡት ስሞታ ትክክል አይደለም የሚሉ የውሳኔ ሀሳቦች ለድምፅ ቀርበው ፣ ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ ያቀረቡት ስሞታ ትክክል ነው መድረኩ አፍኗቸዋል የሚለው ፣ ድጋፍ 3 ፣ ተቃውሞ 510 ፣ ድምፀ ተአቅቦ 4 በመመዝገቡ መድረኩ ብዙ ዕድል ስለሰጣቸው ያቀረቡት ስሞታ ትክክል አይደለም የሚለው ተወስኗል ::

ቀጥሎም ጉባኤው የጉባኤውን ቃለጉባኤ ቁጥር 5 እና 6 መርምሮ ለማፅደቅ ውይይቱን የቀጠለ ሲሆን በቅድሚያ ቃለጉባኤ ቁጥር 5 ተመልክቶ ፣

ገጽ 1 ፣ 12ኛ መስመር "አቶ መሠረት" የሚለው "ወ/ሮ መሠረት"

ገጽ 1 ፣ 17 መስመር "ማስኬቶ" የሚለው "ባስኬቶ"

ገጽ 2 ፣ 2ኛ መስመር "መሐመድ ቤን" የሚለው "መሐመድ ቢን"

ገጽ 2 9ኛ መስመር "ቱፋ ደይቻ" የሚለው "ቱፋ ዶይቻ"

በሚል እንዲስተካከሉ ከተደረገ በኋላ ቃለጉባኤው ከነማሻሻያው ፀድቋል :: የጉባኤው ቃለጉባኤ ቁጥር 6ትም

ገጽ ፣ 9 የአንቀጽ 4 ርዕስ "ለቅጣት የሚያበቡ ምክንያቶች" የሚለው "ለቅጣት የሚያበቁ ምክንያቶች "፣

ገጽ ፣ 13 ፣ 6ኛ መስመር "አቶ አህመድ" የሚለው "አቶ መሀሙድ"

ገጽ 16 ፣ 18ኛ መስመር "አቶ ደስት አጥናፉ" የተባለው "አቶ ደስታ ቁናሳ"

ገጽ 17 ፣ 2ኛ ፓራግራፍ ፣ 3ኛ መስመር "አከ" የሚለው "አከራካሪ"

በሚል እንዲስተካከሉ ጉባኤው ከወሰነ በኋላ ቃለጉባኤ ቁጥር 6 ከነማሻሻያው ጉባኤው አፅድቆታል ።

ከዚያም ጉባኤው በረቂቅ ሕገ መንግሥት አንቀጽ 9 ላይ ውይይቱን የቀጠለ ሲሆን የጉባኤው ሊቀመንበር በቅድሚያ በአንቀጹ የሚጨመር ወይም የሚቀነስ ወይም መሻሻል የሚገባው ነጥቦች ካሉ ሊቀርቡ እንደሚችሉ ገልጸዋል ።

በዚህም መሠረት አቶ ዮሐንስ አሰፋ ከክልል 14 የኢትዮጵያ የሽግግር መንግሥት ወደፊት የሚመረጠው ቋሚ መንግሥት ማድረግ የሚገባውን የኤርትራ መገንጠልና የአባይ ወንዝ ውሉችንና የመሳሰሉትን መዋዋሉ ተገቢ ባለመሆኑ አንቀጽ 9 ንዑስ አንቀጽ 4 ኢትዮጵያ ወደፊት የምታፀድቃቸውን ዓለም አቀፍ ስምምነቶች ብቻ ሊያጠቃልል በሚችል መልኩ እንዲሻሻል ሀሳብ አቅርበዋል ።

ለዚህም የጉባኤው ሊቀመንበር ሲመልሱ የዚህ ጉባኤ አላማ የሽግግር መንግሥቱ ያከናወናቸውን ክንውኖች ለመተቸት ሳይሆን ሕገ መንግሥቱን ማፅደቅ በመሆኑ በዚህ ላይ ማትኮር እንደሚገባ አሳስበዋል ።

በሌላ በኩል ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ ከክልል 14 በኢትዮጵያ በደርግ ጊዜ የተወረሱ ቤቶች ባለመመለሳቸው የመሬት ኪራይ / ሊዝ / አዋጅ በመታወጁና ፍርድ ቤቶችም ነፃነታቸውን አጥተው በጠቅላይ ሚኒስትሩ ትዕዛዝ እንደሚቀሳቀሱ ስለሚነገር ሀገሪቱ የተቀበለቻቸው በርካታ የዓለም አቀፍ ስምምነቶች ስለማይተገበሩና ስለሚጣሱ ይህንን ለመከላከል አንቀጽ 9 ንዑስ አንቀጽ 4 "ኢትዮጵያ ካፀደቀቻቸው ዓለም አቀፍ ስምምነቶች ውጭ የወጡ አዋጆችና ድንጋጌዎች ሁሉ ውድቅ ይሆናሉ ። " በሚል እንዲተካ ሀሳብ አቅርበዋል ።

ቀጥሎም አቶ ታሪኩ ፅጌ ከክልል 14 አቶ ዮሐንስ አሰፋ ከሰነዘሩት ሀሳብ በመነሳት የአባይ ወንዝ ውል ወደፊት የሚመረጠው ቋሚ መንግሥት መዋዋል ሲገባው የሽግግር መንግሥቱ መዋዋሉ ተገቢ እንዳልሆነ ፣ የኤርትራ ከኢትዮጵያ መገንጠል ቅር ሊል ቢችልም ጊዜውን ጠብቆ የተፈጸመ በመሆኑ በጉባኤው ሊነሳ እንደማይገባ ፣ ከተነሳም አንሺውን ሊያስጠይቅ እንደሚችል ጠቁመው የኢትዮጵያና የኤርትራ ሕዝቦች ወደፊት በእግዚአብሔር ፈቃድ ሊዋሃዱ የሚችሉበት አጋጣሚ ሊፈጠር ስለሚችል በወንድማማችነት ሊታያዩ እንደሚገባ አስገንዝበዋል ።

ከዚያም አቶ ዘለሌ ፀጋሥላሴ ከክልል 14 ሕዝብ የሉዓላዊ ሥልጣን ባለቤትና የመንግሥት ሥልጣን ምንጭ መሆኑ በቀደሙት አንቀጾች ተረጋግጦ እንደታለፈና ሕዝብ ለመንግሥት የሚሰጠው ሥልጣን "ተቀመጥ በወንበሬ ተናገር በከንፈሬ" ዓይነት የውክልና ሥልጣን እንደሆነ ፣ መንግሥት በተሰጠው ሥልጣን መሠረት የሕዝብን ሰብአዊና ዲሞክራሲያዊ መብቶች እንዲከበሩ አድርጎ ካላስተዳደረ



ሥልጣኑን ሕዝብ መልሶ እንደሚነጥቀውና በሌላ እንደሚተካው የታወቀ ስለሆነ በዚህ ሕገ መንግሥት ከተደነገገው ውጭ የመንግሥት ሥልጣን መያዝ እንደማይቻል የሚደነግገው አንቀጽ 9 ንዑስ አንቀጽ 3 አላስፈላጊ መሆኑን ገልጸዋል ።

አያይዘውም በአለፉት የአገራችን መንግሥታት የወጡት ሕገ መንግሥቶች ከቤተ መዘክር ጌጥነት አልፈው ለሕዝቡ ተግባራዊ ጠቀሜታ አለመስጠታቸውን አውስተው የአሁኑ መንግሥት ግን በአፈጻጸሙ ተግባራዊ ሊሆን የሚችልና ሕዝቡም የእኔ ነው ብሎ ሊቀበለው የሚገባ መሆን እንዳለበት ፣ በዚህ ረገድም የመንግሥትን ሥልጣን መያዝ የሚችለው በሕገ መንግሥቱ በተደነገገው መሠረት ብቻ ነው ማለት በሌሎች መንገዶችም ሕዝብ ሥልጣን ሊሰጥ የሚችልበትን ስለሚዘጋ እንደማያስፈልግ አመልክተዋል ።

ቀጥሎም አቶ መሐመድ አህመድ ከክልል 3 በበኩላቸው ሕገ መንግሥቱ በኢትዮጵያ ብሔር / ብሔረሰቦች ተወካዮች የሚፀድቅ ሕጎች ሁሉ የበላይና ምንጭ በመሆኑ እያንዳንዱ ዜጋ ባለሥልጣን እንዲሁም በሀገሪቱ የሚንቀሳቀሱ የፖለቲካ ድርጅቶች በግዴታ ሊያከብሩት ስለሚገባ በአንቀጽ 9 ንዑስ አንቀጽ 2 ላይ "ኃላፊነት አለባቸው" የሚለው ሐረግ "ግዴታ አለባቸው" በሚል እንዲተካ ሀሳብ አቅርበዋል ።

ከዚያም አቶ አብዱልቃድር ሙአልም ከክልል 5 ፣ አቶ ዴቪድ አኩዋር ከክልል 12 አንቀጽ 9 ንዑስ አንቀጽ 4 በተመለከተ በሰጡት አስተያየት ሕዝብን ለመፈጀትና ለማጥቃት ብሎም ለመርገጥ ባለፉት ሥርዓቶች የተደረጉ የጦር መሣሪያ ግዢ ውሎችና ለግዢው የተፈረሙ የብድር ስምምነቶች የሀገሪቱ የሕግ አካል ሊሆኑ እንደማይገባ ሀሳብ ያቀረቡ ሲሆን፣ ከዚህም በመነሳት የጉባኤው ምክትል ፀሐፊ የጦር መሣሪያ ግዢና ለግዢው የተደረጉ የብድር ስምምነቶች አንድ ሀገር ከሌላው ሀገር ጋር የሚያደርጋቸው ስምምነቶች በመሆናቸው ከዓለም አቀፍ ስምምነቶች ጋር ሊዛመዱ እንደማይችሉ አስረድተዋል ።

ቀጥሎም አቶ ዳንኤል በላይነህ ከክልል 14 አቶ መሐመድ አህመድ ከክልል 3 በአንቀጽ 9 ንዑስ አንቀጽ 2 ላይ "ኃላፊነት አለባቸው" የሚለው ሐረግ "ግዴታ አለባቸው" በሚል እንዲተካ ያቀረቡት ሀሳብን በመቃወም የወከላቸው 100,000 ያህል ሕዝብ ፍላጎት በሕገ መንግሥቱ እንዲካተት ጠይቀው ተቀባይነት እንዳላገኘና ይህ እስካልሆነ ድረስ የወከላቸው ሕዝብ ፍላጎቱ ያልተካተተበትን ሕገ መንግሥት እንዲያከብር እንዴት ሊገደድ እንደሚችል ግልጽ እንዳልሆነላቸው አመልክተዋል ።

ከዚያም የጉባኤው ሊቀመንበር ከተለያዩ አባላት በቀረቡ የማሻሻያ ሀሳቦች ላይ አስተያየቶች መስጠት እንደሚቻል በገለጹት መሠረት አቶ አወጣ ገብሩ ከክልል 3 አንቀጽ 9 ንዑስ አንቀጽ 4 ወደፊት ቋሚው መንግሥት የሚፈርማቸው ዓለም አቀፍ ውሎች በሚያጠቃልል መልኩ እንዲሻሻል የቀረበው ሀሳብ የሽግግር መንግሥት ያከናወናቸውን ተግባራት ለመቃወም ካልሆነ በቀር ተገቢ እንዳልሆነ ፣ በቀድሞ ሥርዓቶች የተፈረሙ የጦር መሣሪያ ግዢዎችና ለግዢው የተደረጉ የብድር ስምምነቶች ይኸው አንቀጽ እንዲሻሻል የቀረበው ሀሳብም ስምምነቶቹ በሁለት አገሮች መካከል የተደረጉ እንደመሆናቸው መጠን በዓለም አቀፍ ስምምነቶች ሊጠቃለሉ እንደማይችሉ ገልጸዋል ።

አክለውም አንቀጽ 9 ንዑስ አንቀጽ 3 ለሕዝብ ተወካዮች የተሰጠውን ሥልጣን ከሕዝቡ በስተቀር ማንም ከተወካዩ ሊነጥቅ እንደማይችል እንደሚያመለክት ፣ ከዚህም አኳያ የሕዝብን ሉዓላዊነት የበለጠ የሚያረጋግጥ በመሆኑ እንዲወጣ ከአቶ ዘለሌ ፀጋሥላሴ ከክልል 14 የቀረበው የማሻሻያ ሀሳብ ተገቢ እንዳልሆነ ገልጸው ለሕገ መንግሥቱ ተገዢ የመሆንና የማስከበር ኃላፊነቱን ያልተወጣ ኢትዮጵያዊ ዜጋ በሕግ መጠየቁ ስለማያጠራጥር በአንቀጽ 9 ንዑስ አንቀጽ 2 ላይ ኃላፊነት የሚለው ቃል ግዴታ በሚል መተካት እንደሌለበት አመልክተዋል ።

ከዚያም አቶ ተስፋይ ሐጎስ ከክልል 1 አንቀጽ 9 ንዑስ አንቀጽ 1 ሕገ መንግሥቱ ከሌሎች ሕጎች ሁሉ የበላይ መሆኑን የሚደነግግ በመሆኑ እንዳለ እንዲቀመጥ ፣ ኢትዮጵያ የፈረመቻቸው ወይም ለወደፊቱ የምትፈርማቸው ዓለም አቀፍ ስምምነቶች የሀገሪቱ ሕጎች አካል መሆናቸውም ሀገሪቱ ለዓለም አቀፍ ሕጎች ተገዢ መሆንዋን እንደሚያመለክት ፣ ተገዢ የመሆንም ግዴታ እንዳለባት እንዲሁም የጦር መሣሪያ ግዢና ለግዢው የተደረጉ የብድር ስምምነቶች በዓለም አቀፍ ስምምነቶች ሊጠቃለሉ እንደማይችሉ ገልጸዋል ።

አያይዘውም እስከ አሁን የተደረገው የአባይ ወንዝ ውል በአፄ ሚኒሊክ ዘመነ መንግሥት ከግብፅ ጋር የተደረገው ውል ብቻ እንደሆነ ፣ የሽግግሩ መንግሥት ያደረገው ነገር ቢኖር የወንዙን አጠቃቀም በተመለከተ በውሉ ለግብፅ የተሰጠውን የበላይነት የሚቀንስ የመግባቢያ ሀሳብ /Memorandum of UnderstaNding / እንደሆነ ጠቀመው የኢትዮጵያ የግዛት ወሰን የፌዴራል አባሎች ወሰን እንደሚያጠቃልል ቤቱ ያፀደቀ ስለሆነ የኤርትራ ጉዳይ በጉባኤው መነሳት እንደሌለበት አውስተዋል ።

ከዚያን አቶ አህመዲን ኢብራሂም ከክልል 4 በበኩላቸው በአንቀጽ 9 ንዑስ አንቀጽ 2 ላይ "ኃላፊነት አለባቸው" የሚለው ሐረግ "ግዴታ አለባቸው" በሚል እንዲተካ የሚለው ሀሳብ "ኃላፊነት" የሚለው ቃል "ግዴታ" በሚለው ቃል ቢተካ





በሁለቱ ቃላት መካከል ሰፊ ልዩነት እንደሚታይ ፣ እንዲሁም አንቀጽ 9 ንዑስ አንቀጽ 3 የሕዝብን ሥልጣን ከተወካዩ በኃይል መንጠቅ የሚከለክልና የሕዝብን ሉዓላዊነት የሚያረጋግጥ በመሆኑ ሁለቱ ንዑሳን አንቀጾች እንዳሉ ቢቀመጡ እንደሚሻል ገልጸዋል ።

አስከትለውም ኢትዮጵያ ያፀደቀቻቸው ዓለም አቀፍ ስምምነቶች ብሔራዊ ጥቅሟን የሚያስጠብቁ ቢሆንም ሌላ ተጨማሪ ግዴታ ሊያስከትሉ እንደሚችሉ ፣ ግዴታውንም መቀበል እንዳለባት ፣ ስምምነቶቹን ካለተቀበለች አሉታዊ ውጤት ሊያስከትሉ እንደሚችሉ መገንዘብ እንደሚያስፈልግ ፣ ስምምነቶቹ አገሪቱ ከምታራምደው ፖሊሲ አኳያ ለሕዝብ ጥቅም ሲባል ሕዝብን የሚወክለው መንግሥት በሚያደርገው ዓለም አቀፋዊ ግንኙነት አማካይነት ሊሰረዙ ወይም ሊሻሻሉ እንደሚችሉ ጠቀመው አንቀጽ 9 ንዑስ አንቀጽ 4 ወደፊት አገሪቱ የምታፀድቃቸው ዓለም አቀፍ ስምምነቶች እንዲያጠቃልል ያፀደቀቻቸው ከሚለው ቀጥሎ እና የምታፀድቃቸው የሚል ሐረግ እንዲጨመርበትና ተቀባይነት ሊያገኝ እንደሚገባ አሳስበዋል ።

ቀጥሎም አቶ ዘለሌ ፀጋሥላሴ ከክልል 14 አንቀጽ 9 ንዑስ አንቀጽ 3 እንዲወጣ ያቀረቡት ሀሳብ ከዚህ በፊት ጉባኤው ስለሕዝብ ሉዓላዊነት ሲወያይ ያለ ሕዝብ ፍላጎት ሥልጣን በኃይል መያዝ እንደማይቻል መገለጽ አለበት በሚል ያቀረቡትን ሀሳብ እንደሚቃረን ፣ለማንኛውም ግን አንቀጹ በሕዝብ ፈቃድ ካልሆነ በቀር በሌላ በማንኛውም መንገድ ሥልጣን መያዝ እንደማይቻል ስለሚደነግግ አስፈላጊ እንደሆነ ገልጸዋል ።

አክለውም ሕገ መንግሥቱን የሚቃረኑ ስምምነቶች እንደማይፈጸሙና ሕጎችም እንደማይወጡ ጠቀመው "ኢትዮጵያ ያፀደቀቻቸው ዓለም አቀፍ ስምምነቶች ውጭ የወጡ ድንጋጌዎችና አዋጆች ሁሉ ውድቅ ይሆናሉ ። " በሚል ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ ካቀረቡት ማሻሻያ ይልቅ በአንቀጽ 9 ንዑስ አንቀጽ 4 ላይ የተቀመጠው አገላለጽ የተሻለ እንደሆነ አብራርተዋል ።

አቶ ዘለሌ ፀጋሥላሴ አንቀጽ 9 ንዑስ አንቀጽ 3ን በሚመለከት ያቀረቡት ሀሳብ ቀደም ሲል ሕዝብ ሉዓላዊነት እንዳለው ካቀረቡት ሃሳብ አቶ ታደሰ ካሳ ያቀረቡትን ሀሳብ በመቃወም አቶ ዘለሌ ፀጋሥላሴ ከክልል 14 ቤቱ በሕዝብ ሉዓላዊነት ላይ ሲወያይ ያቀረቡት ሀሳብ ሕዝቡ የሥልጣን ባለቤትነቱን አሳልፎ የሰጠው ሥልጣን አንድ ባለሥልጣን ያለ ሕዝብ ፈቃድ ሥልጣኑን ሊነጥቅ አይችልም የሚል እንደሆነ አንቀጽ 9 ንዑስ አንቀጽ 3 ላይ ያቀረቡት ሀሳብ ግን ባለሥልጣኑ ሥልጣኑን

ያለአግባብ ከተጠቀመ ሥልጣኑን በሕዝብ ሊነጠቅ ይችላል በሚል እንደሆ የማስተካከያ ሀሳብ አቅርበዋል ::

ከዚያም በአንቀጽ 9 ንዑስ አንቀጽ 2 ላይ "ኃላፊነት" የሚለው ቃል "ግዴታ" በሚል ቃል እንዲተካ ሀሳብ ያቀረቡት አቶ መሀመድ አህመድ ከክልል 3 ከተደረገላቸው ማብራሪያ በቂ ግንዛቤ ስላገኙ ሀሳባቸው እንዳነሱ የገለጹ ሲሆን አንቀጽ 9 ንዑስ አንቀጽ 3 እንዲወጣ በአቶ ዘለሌ ፀጋሥላሴ የቀረበውን ሀሳብ በመደገፍ ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ ከክልል 14 የቀደምት ሁለት ሥርዓቶች ባለሥልጣናት በሥልጣን ዘመናቸው ሥልጣናቸው ከእኛ አይወጣም በሚል በየሕገ መንግሥታቸው ቢያስቀምጡም ሥልጣናቸውን በሕዝብ መነጠቃቸው አለመቅረቱ ሲታይ አሁን ይህንን ድንጋጌ በአሁኑ ሕገ መንግሥት ማስቀመጡ አላስፈላጊ እንደሆነ አመልክተዋል ::

በሌላ በኩል የቀረበውን ሀሳብ በመቃወም አቶ አሰፋ ቀናው ከክልል 4 አንቀጽ 9 ንዑስ አንቀጽ 3 የሕዝቡን ሉዓላዊነትና የሥልጣን ምንጭነቱን የሚያረጋግጥና ሥልጣን በኃይል መያዝ አይቻልም እንጂ አምባገነንነት ይቀጥላል የሚል ባለመሆኑ እንዳለ እንዲቀመጥ ሀሳብ አቅርበዋል ::

ከዚያም አንቀጽ 9 ንዑስ አንቀጽ 3 እንዲወጣ በአቶ ዘለሌ ፀጋሥላሴ የቀረበው ሀሳብ ለድምፅ ፣ ድጋፍ 2 ፣ ተቃውሞ 505 ፣ ድምፀ ተአቅቦ 3 በመመዝገቡ አንቀጽ 9 ንዑስ አንቀጽ 3 ባለበት መልኩ እንቀመጥ ተቀባይነት አግኝቷል ::

በሌላ በኩል አንቀጽ 9 ንዑስ አንቀጽ 4 የተደረጉት የጦር መሣሪያ ግዢና ለግገርው የተፈረሙ የብድር ስምምነቶችን በሚያጠቃልል መልኩ ይቀመጥ ያሉት የጉባኤው አባል ሀሳባቸውን አንስተዋል ::

እንዲሁም አንቀጽ 9 ንዑስ አንቀጽ 4 ላይ "ኢትዮጵያ ያፀደቀቻቸው" የሚለው ሐረግ "የምታፀድቃቸው" የሚል ቃል እንዲታከልበት ያሉት አባልም ሀሳባቸውን አንስተዋል ::

ቀጥሎም አንቀጽ 9 ንዑስ አንቀጽ 4 "ወደፊት የኢትዮጵያ ቋሚ መንግሥት የሚያፀድቃቸው ስምምነቶች የሀገሪቱ ሕግ አካል ይሆናሉ" በሚል እንዲሻሻል አቶ ዮሐንስ አሰፋ ያቀረቡት ሀሳብ ለድምፅ ቀርቦ ፣ ድጋፍ 2 ፣ ተቃውሞ 505 ፣ ድምፀ ተአቅቦ 3 በመመዝገቡ የቀረበው ማሻሻያ ሀሳብ ውድቅ ሆኗል ::

ከዚያም ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ በአንቀጽ 9 ንዑስ አንቀጽ 4 ላይ «ኢትዮጵያ ካፀደቀቻቸው ዓለም አቀፍ ስምምነቶች ውጭ የወጡት አዋጆችና ድንጋጌዎች ሁሉ ውድቅ ይሆናሉ» የሚለው ማሻሻያ ሀሳብ ለድምፅ ቀርቦ ፣ ድጋፍ 4 ፣ ተቃውሞ 504 ድምፀ ተአቅቦ 1 በመመዝገቡ ማሻሻያ ሀሳቡ ውድቅ ሆኗል ::



በመጨረሻም አንቀጽ 9 እንዳለ ይቀመጥ የሚለው የውሳኔ ሀሳብ ለድምፅ ቀርቦ ድጋፍ 505 ፣ ተቃውሞ 3ና ያለምንም ድምፀ ተአቅቦ ተቀባይነት አግኝቶ ጉባኤው ከቀኑ በ7:00 ሰዓት ለምሳ ተነስቷል ::

ኅዳር 3 ቀን 1987 ዓ.ም ከሰዓት በኋላ በ9:10 የቀጠለው የሕገ መንግሥት ጉባኤ ስብሰባ በቅድሚያ የጉባኤው ዋና ፀሐፊ ከ500 በላይ የጉባኤ አባላት የተገኙ ስለሆነ ጉባኤው ውይይቱን ሊቀጥል እንደሚችል ከገለጹ በኋላ የጉባኤው ሊቀመንበር ጉባኤው ውይይቱን ሰብአዊና ዲሞክራሲያዊ መብቶ በሚለው በአንቀጽ 10 ሥር በተካተቱት ሁለት ንዑስ አንቀጾች ላይ እንደሚጀምር ገልጸው አንቀጾችን በንባብ አስምተዋል ::

አያይዘውም አንቀጽ 10 የሕገ መንግሥት መሠረታዊ መርሆዎች በሚለው በምዕራፍ 2 ሥር የሚገኝና ሕገ መንግሥቱን የሚፀድቀው በምን መንፈስና መርሆዎች ላይ ተመሥርቶ መሆን እንዳለበት የሚያመለክትና በሕገ መንግሥቱ መሠረት የምትመሠርተው ኢትዮጵያ ምን ዓይነት መሆን እንደሚገባት የሚያሳይ መሆን የጠቆሙ ሲሆን በሥሩ ባሉት ሁለት ንዑሳን አንቀጾች የተካተቱት ነጥቦች በዓለም አቀፍ ደረጃ ተቀባይነት ያላቸው በመሆናቸው ብቻ ሳይሆን ከራሳችን ታሪክና ሕይወት ተነስተንም በሕገ መንግሥቱ መቀረጻቸውን ልናምንበት ይገባል በማለት አስገንዝበው በአንቀጽ 10 ላይ ተቃውሞ ፣ የሚጨመር ፣ የሚቀነስ ወይም የሚወጣ ነገር ካለ አስተያየት እንዲቀርብ ቤቱን አሳስበዋል ::

በዚህም መሠረት አቶ አዳሙ ደገፉ ከክልል 14 የሰው ልጅ በአመዛኙ ሰብአዊ መብቱ ያለተከበረበትና የሰብአዊ መብቶች መከበር በወረቀት ላይ ቢፃፍም በተግባር ግን መብቶቹ የተረገጡበት ዕውነታ ጎልቶ ስለሚታይ ይህን ሁኔታ ለማስወገድ የሚረዳው አንቀጽ 10 ቀላል ግምት ሊሰጠው እንደማይገባ ገልጸው ከጉዳዩ ክብደት አንፃር ሁለቱ ንዑስ አንቀጾች ማለትም ፣

1. ሰብአዊ መብቶችና ነፃነቶች ከሰው ልጅ ተፈጥሮ የሚመነጩ ፣ የማይጣሱና የማይገፈፉ ናቸው ::
2. የዜጎችና የሕዝቦች ሰብአዊና ዲሞክራሲያዊ መብቶች ይከበራሉ ::

የሚሉት በቂ ስላልሆኑ ሰብአዊ መብቶችና ነፃነቶች እንዴት እንደሚከበሩ ሕገ መንግሥታዊ ዋስትና የሚያገኙበትን መንገድ ቤቱ ተወያይቶ ቢጨምርበት አለዚያም የራሳቸውን ማሻሻያ ሊያቀርቡ እንደሚችሉ አስገንዝበዋል ::

ሆኖም የሰብአዊ መብቶች አከባበር ጉዳዩ እንዴት ሊፈጸም እንደሚችል በመሠረታዊ መርሆዎች ሥር እንደማይቀመጥ የጉባኤው ሊቀመንበር ጠቁመው አፈጻጸሙ የግድ መጨመር አለበት ከተባለ ግን እንደሚቻል ገልጸዋል ።

በዚህም መሠረት አቶ አዳሙ ደገፉ "በዚህ መሠረት በመንግሥት ሆነ በፓርቲ ወይም በመንግሥታዊ አካል ከዚህ ሕገ መንግሥታዊ ዋስትና ውጭ መፈጸም አይችልም ። "የሚል ንዑስ አንቀጽ 3 ሆኖ ቢገባ ለጉዳዩ ክብደት እንደሚሰጠው አመልክተዋል ።

ከዚያም የጉባኤው ሊቀመንበር አንቀጹ እንዲሻሻል ወይም እንዲለወጥ ተጨማሪ አስተያየት እንዲቀርብ ጠይቀው ባለመኖሩ አንቀጹን በመደገፍ ወይም የቀረበውን ተጨማሪ አንቀጽ በመመርኮዝ አስተያየ እንዲሰጥ አሳስበዋል ።

በዚህም መሠረት አቶ ኩማ ደመቅሳ ከክልል 4 ሰብአዊ መብቶች በመንግሥት ወይም በፓርቲ ይነጠቃሉ የሚለው ሥጋት ሊመጣ የሚችለው የሚቋቋመው መንግሥት አምባገነንና መብት ረጋጭ ሲሆንና ሕዝቡም መብቱን የረገጠውን መንግሥት አውርዶ በሌላ መተካት የማይችል ሲሆን እንደሆነ ፣ በሚፀድቀው ሕገ መንግሥት ግን የሉዓላዊ ሥልጣን ባለቤት ሕዝብ እንደሚሆንና ማንም ፓርቲ ወይም የመንግሥት አካል ሰብአዊ መብትን ሊረግጥ ቢሞክር ሕዝቡ ከሥልጣኑ አውርዶ ፍርድ ሊሰጠው የሚችል መሆኑ በግልጽ እንደተቀመጠና ከዚህ ውጭ ሌላ የሰብአዊ መብቶች ዋስትና ሊኖር እንደማይችል ፣ በመሆኑም በአንቀጽ 10 ይጨመር የተባለው ንዑስ አንቀጽ 3 እንደማያስፈልግ በረቂቁ የተቀመጠው እንዳለ ቢያልፍ እንደሚመረጥ ሀሳብ አቅርበዋል ።

በመጨረሻም አንቀጽ 10 እንዳለ እንዲፀድቅ ለድምፅ ቀርቦ ፣ ድጋፍ 490 ፣ 1 ተቃውሞና ያለምንም ድምፀ ተአቅቦ ፀድቋል ።

ቀጥሎም ጉባኤው የመንግሥትና የሃይማኖት መለያየት በሚለው አንቀጽ 11 ላይ ውይይቱን የቀጠለ ሲሆን ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ ከክልል 14 "መንግሥት በሃይማኖት ጉዳይ ላይ ጣልቃ አይገባም ። ሃይማኖትም በመንግሥት ጉዳይ ላይ ጣልቃ አይገባም ። "የሚለው አንቀጽ 11 ንዑስ አንቀጽ 3 በተመለከተ መንግሥት የሚገዛው በሕገ መንግሥት ሲሆን ሃይማኖት ደግሞ በሕገ እግዚአብሔር ከመሆናቸው አኳያ መንግሥት በሃይማኖት ጣልቃ አለመግባቱ ተገቢ ቢሆንም ሃይማኖት ግን ሕገ እግዚአብሔር ሲጣስ ፣ በመጽሐፍ ቅዱስ ወይም በቁርዓን የተቀመጠውን የሃይማኖት ሕግ በሚቃረን መልኩ ሕገ መንግሥት ሲወጣ ዝም ብላ መመልከት ሳይሆን እምቢ በማለት ለሕገ እግዚአብሔር መስዋዕት መሆን እንደ





ሚጠበቅባት አሳስበው ለምሳሌ በመጽሐፍ ቅዱስ "የወንድምህን ቤቱን ፣ ንብረቱን አህያውን አትመኝ" የሚለው ቃል የምታስተምረው ቤተክህነት ደርግ ባወጣው አዋጅ ግለሰቦች በወዛቸው የሠሩትን ቤታቸውን ሲነጠቁ ዝም ብላ እንደተመለከተች ፣ እንደዚሁ ዓይነቱ ሕገ እግዚአብሔር ሲጣስ ዝም የማለት ሁኔታ ግን ከማንኛውም ሃይማኖትና ሃይማኖት ተከታይ እንደማይጠበቅ ፣ ወደፊትም ቢሆን ሃይማኖት በመግሥት ጉዳይ ጣልቃ አይገባም በሚል መንግሥት ሕገ እግዚአብሔርን የሚሻረር ሰይጣናዊ ሕግ ሲያወጣ ቤተክርስትያን ሆነ መስጊድ በዝምታ ማለፍ እንደሌለበት አሳስበዋል ።

ከዚያም አቶ ሸምሰዲን አህመድ ከክልል 5 ከዚህ ቀደም መንግሥትና ሃይማኖት ተባብረው በልዩ ልዩ ሃይማኖት ተከታዮች ላይ ከፍተኛ በደል ሲፈጽሙባት በነበረችው ኢትዮጵያ ፣ የአንድ ሃይማኖት ተከታዮች ብቻ እንደ ዜጋ ሌሎች በተለይም እስላሞች ከውጭ ሀገር መጥተው በእንግድነት እንደተቀመጡ በመቁጠር ከፍተኛ የእምነት ዲሞክራሲ መብት ረገጣ ይካሄድባት በነበረችው አገራችን መንግሥትና ሃይማኖት ኦፊሴላዊ ግንኙነት እንደሌላቸው የሚደነግገው አንቀጽ 11 ለሀገሪቱ መሠረታዊ ለውጥ የሚያመጣ የእምነት ነፃነትን የሚያጎናፅፍ በሃይማኖታቸው ምክንያትም ሲረገጡ ለኖሩ ሕዝቦች ትልቅ እፎይታ ስለሆነ እንዳለ መፅደቅ እንደሚገባው አመልክተዋል ።

አያይዘውም በአንቀጽ 11 ንዑስ አንቀጽ 1 «መንግሥትና ሃይማኖት የተለያዩ ናቸው" ሲባል ማንኛውም ሃይማኖት በራሱ ነፃነት እንደሚቀሳቀስና መንግሥትም የራሱን ተግባር ብቻ እንደሚያከናውን ፣ በደርግ ጊዜ እንደተደረገው የሃይማኖት መሪዎች ሳይቀሩ በመንግሥት የሚሾሙበት ሁኔታ እንደማይኖር ማመልከቱ እንደሆነ ፣ በተጨማሪም በሀገሪቱ ውስጥ ካሉት ሃይማኖቶች መካከል አንዱ ተመርጦ መንግሥታዊ በመሆን ማንኛውም መብት የሚጎናጸፍበት ሌሎች ሃይማኖቶችና ተከታዮቻቸው በእምነታቸው ምክንያት የሚረገጡበት ሁኔታ እንዳይኖር ማስረገጥ መሆኑን አስረድተው በአንቀጹ ለማስቀመጥ የተፈለገው ዋናው ጉዳይ መንግሥት አለማዊ / Secular / መሆኑን ማሳየት እንደሆነና የፈለጉትን ሃይማኖት የመከተሉ ዲሞክራሲያዊ መብት ሕገ መንግሥታዊ ዋስትና የሚያገኝበትን ግን በሌላ አንቀጽ ስለተቀመጠ ጉዳዩ ሲደረስበት መወያየት እንደሚቻል አስገንዝበዋል ።

ቀጥሎም አቶ አሊ አብዶ ከክልል 14 ባለፈው የአፄ ኃይለ ሥላሴ መንግሥት "ኢትዮጵያ የክርስትያን ደሴት ናት" በሚል ፈሊጥ የክርስትና ሃይማኖት የመንግሥት አካል በመሆን የመንግሥት ድንጋጌዎች አስፈጻሚ እንደነበር፣ የእስልምና ሃይማኖት ተከታዮች በገዛ አገራቸው እንደ ውጭ ዜጋ የሚቆጠሩበት፣ ሃይማኖታቸውን ለመለወጥ የተገደዱበትና ከፍተኛ የሃይማኖት ጭቆና የተካሄደበት፣ በደርግ ጊዜም አምልኮ ጭራሽ የተከለከለበት ሁኔታ እንደነበር ገልጸው የእምነት ነፃነት ከግለሰብ ሰብአዊ መብቶች አንዱና በተፈጥሮ ሰው በመሆን የሚገኝ ከሌላ አካል በችሮታ የሚሰጥ ባለመሆኑ በአገራችን የተፈጸመው ሃይማኖትን የማበላለጥ ድርጊት ይህንን መብት የሚጻረር እንደነበር አመልክተዋል ፡፡

አክለውም ሃይማኖት ሰማያዊ በመሆኑ ከአለማዊ ሁኔታዎች / መንግሥት፣ ብሔር / ብሔረሰብ ፣ ቋንቋ / ጋር ተያይዞ መታየት እንደሌለበት ጠቁመው እንደ ኢትዮጵያ ባሉ የተለያዩ ሃይማኖት ተከታዮች ባሉባቸው አገሮች ካሉት ሃይማኖቶች መካከል አንዱን መርጦ የመንግሥት ማድረግ አስቸጋሪና አድላዊነትን መፍጠር ስለሚሆን የመንግሥትና የሃይማኖት መለያየትና መንግሥታዊ ሃይማኖት አለመኖር የግድ መደረግ ያለባቸው አስፈላጊ ሁኔታዎች እንደሆኑ አስገንዝበዋል ፡፡ "መንግሥት በሃይማኖት ጉዳይ ጣልቃ አይገባም" ሲባል በመንግሥትነቱ የሃይማኖት ሥራ እንደማይሠራ ፣ የመንግሥት ሠራተኞችም የግል እምነታቸውን ሊያራምዱ የሚችሉት ከመንግሥታዊ ሥራ ውጭ እንደሆነ እንደሚያመለክትና "ሃይማኖት በመንግሥት ጉዳይ ጣልቃ አይገባም" ሲባልም የአንድ ሃይማኖት ክፍል ተነስቶ የራሱን ሃይማኖት ብቻ ሌሎች በጫና እንዲቀበሉት ለማድረግ መንግሥትን በመዝለት ውይም በሌላ መንገድ ተፅዕኖ ለማድረግ እንዳይሞክር ማስረገጥ መሆኑን፣ መንግሥትና ሃይማኖት ራሳቸውን ችለው በየራሳቸው መንገድ ለመጓዝና ብሎም የግለሰቦች የእምነት ነፃነት ሊከበር የሚችለው 3ቱም ንዑሳን አንቀጾች እንዳሉ ፀድቀው በማለፍ ተግባራዊ ሲሆኑ እንደሆነ አብራርተዋል ፡፡

በማስከተልም አቶ ካህሳይ አለሙ ከክልል 1 በኃይለ ሥላሴ መንግሥት የእስልምና ሃይማኖት ተከታዮች በሃይማኖታቸው ምክንያት መጨቆናቸውን በደርግ ጊዜ ሁለቱንም ማለትም እስልምናና ክርስትና ሃይማኖቶች እንዲጠፉ ተደርጎ እንደነበር ፣ ባለፉት ሥርዓቶች የእስልምና ሃይማኖት ተከተታዮችና ብሔር/ ብሔረሰቦች የሕግ መንግሥት ጉባኤ በመሰለ ታላቅ መድረክ መሳተፍ ይቅርና ደክመው ያፈሩትን እንጀራ ለመብላት እንኳን የቱን ያህል መሸማቀቅ ይደርስባቸው እንደነበረ አስታውሰው በአሁኑ ሰዓት ግን ሁኔታው ተለውጦና የሃይማኖት እኩልነት ተከብሮ የእስልምና ሃይማኖት ተከታዮች ከጭቁን ብሔር/ብሔረሰቦችና ሕዝቦች





ወንድሞቻቸውና እህቶቻቸው ጋር የሚገናኙበት ሁኔታ ተፈጥሮ ለማየት ያበቃውን የጭቁን ሕዝቦችን ትግል አመስግነዋል ፡፡

አያይዘውም በፊት ሃይማኖትን በመለያየት ይጠቀሙ የነበሩ ክፍሎች ይህን ድል ባለመፈለግ በሃይማኖት ሰበብ ለማደናቀፍ መሞከራቸው ስለማይቀር መታገልና ባለው ሕግም መፋረድ እንደሚገባ ገልጸው አንቀጽ 11 በረቂቁ በተቀመጠው መልኩ እንዲጸድቅ አሳስበዋል ፡፡

አቶ ወይናቶ አበራ ከክልል 12 በበኩላቸው የአንቀጽ 11 ንዑስ አንቀጾች አቀራረጽ ተገቢ እንደሆነ ገልጸው በተጨማሪ ግን በሃይማኖቶች ተከታዮች መካከል ግጭት ሲፈጠር መገላገል እንዲችል ፣ "በሁለት ሃይማኖቶች መካከል ችግር ሲፈጠር መንግሥት ጉዳዩን ማየት ይችላል ፡፡" የሚል ቢገባ ለሃይማኖት ነፃነት አመቺ ሁኔታ ስለተፈጠረ አዳዲስ ሃይማኖቶችም መከሰታቸው ስለማይቀር የመንግሥት ገላጋይነት እንደሚረዳ አመልክተዋል ፡፡

ከዚያም ሐጂ አህመድ መንዛሮ ሐጂ ከክልል 4 በኃይለ ሥላሴ መንግሥት ሁለት ሃይማኖቶች ማለትም እስልምናና ክርስትና ብቻ እንደሚታወቁ ፣ ከእነዚህም መካከል ክርስትናን ወደ ራሱ ማስጠጋትና እስልምና ዝቅ በማድረግ የሁለቱ ሃይማኖቶች ተከታዮች ወንድማማች ብሔር/ ብሔረሰቦች አንዱ የበላይ ሌላው የበታች በመሆን ስሜት እንዲተያዩ እርስ በርሳቸው እንዲጋጩና እንዲለያዩ ያደርግ እንደነበር ፣ ሆኖም ሃይማኖት በእግዚአብሔር ፊት እኩል መሆኑንና መስማማትን እንዲሁም ማመስገን እንጂ መጣላትን ስለማይፈቅድ የተፈጸመው ድርጊት ተገቢ እንዳልነበረ ገልጸዋል ፡፡

አክለውም በደርግ መንግሥት ጊዜም ደግሞ ከበፊቱ በባሰ ሁኔታ ሁለቱም ሃይማኖቶች እንዲጠፉ እንደተሞከረ ፣ ስለሃይማኖት የተናገሩ ሰዎች ኅታቾች እየተባሉ ለእስራት እንደተዳረጉ ፣ አሁን ግን በአንቀጽ 11 ንዑስ አንቀጽ 3 እንደተቀመጠው መንግሥት በሃይማኖት ፣ ሃይማኖት በመንግሥት ጉዳይ ጣልቃ እንደማይገቡ መረጋገጡ በተለይ ለእስልምና ሃይማኖት እንደገና እንደመፈጠር ፣ ለተከታዮቹም ዳግም እንደመወለድ እንደሚቆጠር ፣ የክርስትናም ሆነ የሌሎች ሃይማኖቶች ተከታዮችም ከመንግሥት ማስፈራራትና ተፅዕኖ ነፃ ወጥተው በእምነታቸው የመኩራት ዕድል እንደተከፈተላቸው አመልክተው መንግሥት በሃይማኖት ጉዳይ ገብቶ አንዱን ከፍ ሌላውን ዝቅ ማድረጉን ትቶ ሃይማኖትን ለባለሃይማኖቱ እንዲተው መደረጉና ይህ ዲሞክራሲያዊ መብትም በሕገ መንግሥት እንዲረጋገጥ ራሱ ሕዝቡ ባንድ ላይ ተሰብስቦ ማፅደቅ መቻሉ ታላቅ እንደሆነ

አስረድተው ከዚህ አንፃር አንቀጽ 11 ባለበት መልኩ እንዲፀድቅ ሀሳብ አቅርበዋል ::

ከዚያም የጉባኤው ሊቀመንበር አንቀጽ 11 በረቂቁ በተቀመጠው መልኩ እንዲፀድቅ አስተያየቶች መቅረባቸውን ገልጸው የተቃውሞ ሀሳብ ከሌለ በሃይማኖቶች መካከል ግጭት ሲፈጠር ምን መደረግ እንደሚቻል የሕግ አስተያየት ከተሰጠበት በኋላ አንቀጹ በድምፅ እንዲፀድቅ ሀሳብ አቅርበዋል ::

በዚህም መሠረት አቶ አህመዲን ኢብራሂም ከክልል 4 መንግሥት በሃይማኖት ጉዳይ ጣልቃ አይገባም ሲባል በሃይማኖት የቀን ተቀን ተግባር አመራረጡ ይህ ወይም ያ መሆን አለበት ፣ አትፀልዩ ወዘተ... አይልም ማለት መሆኑን ገልጸው በሁለት ወይም ከዚያ በላይ ሃይማኖቶች መካከል ግጭት ከተነሳ ግን በፖሊስ ኃይልና በመከላከያ ሠራዊት አማካይነት ሰላም እንዲከበር ከማድረግ ይቆጠባል ማለት እንዳልሆነ ፣ ሰላም ማስከበርም ሆነ ሕገ መንግሥቱን መጠበቅ በራሱ በሕገ መንግሥቱ ለመንግሥት የተሰጠው ኃላፊነት እንደሆነ አስረድተዋል ::

በሌላ በኩል ደግሞ "ሃይማኖት በመንግሥት ጉዳይ ጣልቃ አይገባም" ማለት በፖሊሲና በመንግሥት የፖለቲካ ሥራ እንደማይገባ እገዳ ተደረገበት እንጂ ሃይማኖታዊ ትምህርት የማስተማር ወዘተ... መብቱን ተከለከለ ማለት እንዳልሆነ አመልክተው ሦስቱ ንዑሳን አንቀጾች አቀራረጻቸው ተገቢ ስለሆነ እንዳለ ቢፀድቅ እንደሚጠቅም ገልጸዋል ::

ከዚያም አንቀጽ 11 ለውሳኔ ቀርቦ ሦስቱ ንዑስ አንቀጾች ያለምንም ማሻሻያ ይፅደቁ የሚለው ድጋፍ 487 ፣ ማሻሻያ ያስፈልገዋል የሚል 2 ፣ ያለምንም ድምፀ ተአቅቦ አንቀጹ እንዳለ ፀድቋል ::

ቀጥሎም የጉባኤው ሊቀመንበር "የመንግሥት አሠራርና ተጠያቂነት ::" የሚለው አንቀጽ 12 ለቤቱ በንባብ አሰምተው በሦስቱ ንዑስ አንቀጾች አስተያየት ካለ እንዲቀርብ ጋብዘዋል ::

በዚህም መሠረት አቶ ሸምሰዲን አህመድ ከክልል 5 "የመንግሥት አሠራር ለሕዝብ ግልጽ በሆነ መንገድ መከናወን አለበት ::" ከሚለው አንቀጽ 12 ንዑስ አንቀጽ 1 ውስጥ " ግልጽ በሆነ መንገድ "የሚለው ከሦስቱ የመንግሥት አካላት አንፃር ምን ማለት እንደሆነና "ሕዝቡ በመረጠው ተወካይ እምነት ባጣ ጊዜ ከቦታ ለማንሳት ይችላል :: ዝርዝሩ በሕግ ይወሰናል :: " ከሚለው ንዑስ አንቀጽ 2 ውስጥ "እምነት ባጣ ጊዜ " የሚለው ሐረግ ምን ማለት እንደሆነ እንዲብራራላቸው ጠይቀዋል ::



ለእነዚህም ጥያቄዎች አቶ አህመዲን ኢብራሂም ከክልል 4 በሰጡት ምላሽ በሕገ መንግሥቱ እንደተቀመጠው መንግሥት ተጠሪነቱ ለሕዝብ ስለሆነና በርግጥም በትክክል የሚያገለግል መሆኑ እንዲታወቅ አሠራሩ ሁሉ ግልጽ መሆን አለበት ማለት እንደሆነ ገልጸው ይህ ሲባል የመንግሥት አካላት ስለአሠራራቸው በየጊዜው ሪፖርት ያቀርባሉ ማለት ሳይሆን ሕዝብ እንዲገለጽለት በፈለገ ጊዜ ይፋ ጋዜጣዊ መግለጫ እንደሚሰጡና ያለፈው ድብቅ አሠራር እንዲቀር የሚያመለክት የሕዝብ መብት ማረጋገጫ መሆኑን አብራርተዋል ::

አያይዘውም ሕዝብ በመረጠው ተወካይ ላይ እምነት ባጣ ጊዜ እንደሚያነሳው የሚገልጸውም በተጠረጠረ ጊዜ ሁሉ ይነሳል ማለት ሳይሆን ተወካዩ ከተመረጠበት ውጭ ሲሠራ ፣ ሥነ ምግባር የጎደለው ድርጊት ሲፈጽም ሕዝብ እምነት እንደሚያጣና ይህ ከሆነም እንደመረጠው ሁሉ ያወርደዋል ማለት መሆኑን አመልክተዋል ::

ከዚያም ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ ከክልል 14 በኃይለ ሥላሴ ዘመን በሕገ መንግሥቱ "ዝርዝሩ በሕግ ይወሰናል ::" የሚል ከተቀመጠ በኋላ ሕጋዊ ያልሆኑ ሕጎች በማውጣት ሕዝቡን እንዳሰቃዩት ፣ አንዳንዶቹም ጭራሽ እንደቀሩ ፣ ለምሳሌ የአገር ውስጥ ገቢ መሥሪያ ቤት ባወጣው ደንብ መሠረት አንድ ነጋዴ ግብር በዛብኝ ብሎ ይግባኝ ለመጠየቅ ቢፈልግ መጀመሪያ 2/3ኛውን ከፍሎ መሆን እንዳለበትና ተከራክሮ ቢረታ እንኳን ገንዘቡ ወደፊት ይታሰባል እንደሚባል እንጂ እንደማይመለስለት ፣ ይህም እንደማንኛውም የፍትሐ ብሔር ጉዳይ የዳኝነቱንና የማስገልበጫውን ክፍሎ ይግባኝ ማለት ያለበትን ሕግ የጣሰ መጨቆኛ መሣሪያ እንደነበር ፣ በሌላ በኩል ደግሞ አንድ የከተማ ከንቲባ የሚሾመው በወጣው ሕግ መሠረት ሦስት ሰዎች ተመርጠው በማቅረብ ለንጉሡ በማስፀደቅ እንደሚሆን በሕገ መንግሥቱ ተቀምጦ የነበረ ቢሆንም ይህ በሕገ መንግሥቱ የተቀመጠው ድንጋጌ በዝርዝር ሕግ ሳይወጣ ንጉሡ እስከ ዕለተ ሞታቸው ድረስ ራሳቸው ከንቲባ እየሾሙ እንደቀጠሉ ፣ በአሁኑ ያለውን ሁኔታ መዘርዘር ባያስፈልግም በርካታ ተመሳሳይ ሁኔታ እንዳለ ገልጸዋል ::

አያይዘውም መንግሥት እምነት ሊጣልበት የማይችል መሆኑን ከረጅም የሕይወት ልምዳቸው እንደተገነዘቡት ፣ በዚህ ሕገ መንግሥት "ዝርዝሩ በሕግ ይወሰናል :: " ተብሎ ቢቀመጥ እንኳን ሕጉ መውጣቱና የሚወጣው ሕግም ለሕዝቡ የሚስማማ መሆኑ ስለማያስተማምን "ዝርዝሩ በሕግ ይወሰናል :: "የሚለው ንዑስ አንቀጽ 2 መሰረዝ እንደሚገባው አሳስበዋል ::

ቀጥሎም አቶ አዳሙ ደገፉ እና አቶ ጀምበሬ ገ/መድህን ከክልል 14 የሻለቃ አድማሴ ዘለቀን ሀሳብ በመደገፍ " ዝርዝሩ በሕግ ይወሰናል :: " የሚለው የሕዝቡን ሉዓላዊነት ለመንግሥት አሳልፎ የሚሰጥ ፣ ሆን ተብሎ ሕዝብን ለመበደል የተቀመጠ ስለሆነ መሰረዝ እንዳለበት አመልክተዋል ::

ከዚያም የጉባኤው ሊቀመንበር ከቀረቡት ሀሳቦች የተለየ ሀሳብ ካለ እንዲቀርብ በገለጹት መሠረት አቶ አባይ ፀሐዬ ከክልል 1 "የመንግሥት አሠራር ግልጽ መሆን አለበት :: " ሲባል በሕዝብ የተመረጠው መንግሥት አሠራር ከሕዝብ ድብቅ መሆን እንደሌለበት የሚያመለክት እንደሆነ ፣ ሕዝብም ስለመንግሥት አሠራር ፣ ውሳኔ ለማወቅ መረጃና ማብራሪያ ቢፈልግ ጠይቆ የመረዳት መብቱ የተጠበቀ መሆኑን ማመልከት እንደሆነ ገልጸዋል ::

አክለውም ሕዝብ በመረጠው ተወካይ ላይ እምነት ባጣ ጊዜ ከቦታው እንደሚያስነሳውና ዝርዝሩም በሕግ እንደሚወሰን ሲገልጽ ደግሞ ሕዝብ በመረጠው ተወካይ ላይ እምነት ሲያጣ ማለትም ተወካዩ መራጩ ሕዝብ እንደፈለገው ሳይሠራ ሲቀር አልፈልግህም ብሎ ሊወርደውና በሌላ ሊተካው መብት ለሕዝብ የሚያጎናጽፍ እንደሆነና ይህ መብትም በዲሞክራሲ በበለጸጉ የምዕራብ አገሮች እንኳን ያልተሰጠ ከፍተኛ መብት መሆኑን አመልክተው ፣ በምዕራብ አገሮች አንድ በሕዝብ የተመረጠ ተወካይ እንዲያገለግል የተመረጠበት 4 ወይም 5 ዓመት የጊዜ ገደብ ካልሞላ ሕዝቡ ቢፈልግም እንኳን ሊያወርደው እንደማይችል ፣ ይህ ሕገ መንግሥት የሚያረጋግጠው ግን ሕዝቡ የተወካዩን የአገልግሎት ጊዜ ሳይጠብቅ እምነት ያጣበት ብቻ በአንድ ሳምንትም ፣ በአንድ ወር ጊዜ ውስጥ ሊያወርደው የሚችል መሆኑን እንደሚያመለክት በመሆኑም ይህ ከፍተኛ የሆነ ዲሞክራሲያዊ መብት ግን በአንዳንድ የጉባኤ አባላት የተሳሳተ ትርጓሜ እንደተሰጠው ገልጸዋል ::

አያይዘውም ባለፉት በአፄዎችም ሆነ በደርግ ሥርዓት አንድ መብት በሕገ መንግሥት ለይስሙላ አውጥተው ነገር ግን ያንን የሚንድ ሕግ ያወጡ ስለነበር በዚህ ሕገ መንግሥት የተቀመጠውም ለይስሙላ ነው የሚል ምክንያት በማቅረብ "ዝርዝሩ በሕግ ይወሰናል :: " የሚለው እንዲሰረዝ ሀሳብ መቅረቡን አውስተው ሕዝቡ ሉዓላዊ ባለሥልጣን እንደሆነ ፣ በሕገ መንግሥቱ መሠረት የሚቋቋመው መንግሥትም ለሕዝብ ግልጽ እንደሚሆንና መንግሥት የማይታመን ነገር ሲፈጽም ሊጠይቀውና ሊያወርደው እንደሚችል በራሱ በሕገ መንግሥቱ ተቀምጦ እያለ ገና የድሮ መንግሥታት አልታመኑምና የወደፊቱ መንግሥትም አይታመንም የሚለው ከመነሻው ስህተት እንደሆነ አብራርተዋል ::



አቶ አባይ ፀሐዬ ማብራሪያቸውን በመቀጠል ሕዝብ በመረጠው ተወካይ ላይ እምነት ባጣ ጊዜ ከቦታው ማንሳት የመቻሉ ዲሞክራሲያዊ መብት በንዑስ አንቀጽ 2 ከተቀመጠ በኋላ ዝርዝር አፈጻጸሙ በሕግ እንደሚወሰን መግለጽ ያስፈለገበት ምክንያት በተወካዩ ላይ እምነት ያጣው ሕዝብ ተወካዩን የሚያነሳበትንና የሚተካበትን አግባብ ሁሉ ለምሳሌ ከቦታው የማንሳቱ ጥያቄ ለማን እንደሚቀርብ ፣ ከሕዝቡ ስንት መቶኛው ሲጠይቅ ተግባራዊ እንደሚሆን ፣ ውሳኔውን ማን እንደሚወስን ፣ ለመተካት ምርጫ እንዴት እንደሚካሄድ ፣ ወዘተ... አጠቃላይ መርሆዎች በሚቀመጡበት ሕገ መንግሥት ዘርዝሮ ማስቀመጥ የማይቻል በመሆኑ እንደሆነ ገልጸው "ዝርዝሩ በሕግ ይወሰናል" የሚለውን ተንተርሶ ወይም የተለየ አላማ ይዞ ጠቅላላ ሕዝብን የሚጎዳ ሕገ መንግሥቱን የሚቃረን ሕግ ከወጣ ተግባራዊ ሊሆን እንደማይችል በራሱ በሕገ መንግሥቱ ተቀምጦ እያለ የአንቀጽ ንዑስ አንቀጽ 2 አቀራረጽ ለይስሙላ መብት በሕግ አስቀምጠው መልሰው ከሚንዱት የኃይለ ሥላሴና የደርግ መንግሥታት ጋር እንዴት ሊነፃፀርና ሥጋት ሊፈጥር እንደቻለ ግልጽ እንዳልሆነላቸው አመልክተዋል ::

ከዚያም ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ ከክልል 14 ኢንፎርሜሽን ለመስጠት ጠይቀው ስለተፈቀደላቸው ይህንን ጉዳይ በተመለከተ ለክልል 14 ምክር ቤት ሀሳብ አቅርበው እንደነበረና አንድ ደንብ ሲወጣ በቅድሚያ አስፈጻሚው አካል አይቶት ትክክል ነው ካላለ በስተቀር አቶ ተፈራ ዋልዋ እንደማይፈርሙና ሕግም እንደማይሆን ገልጸዋል ::

ቀጥሎም የጉባኤው ሊቀመንበር የቀረበው ኢንፎርሜሽን ቤቱ ከጉዳዩ ጋር ይያያዛል ካለ ሊቀበለው እንደሚችል ገልጸው በአንቀጽ 12 ንዑስ አንቀጽ 2 ላይ "ዝርዝሩ በሕግ ይወሰናል :: " የሚለው እንዲሰረዝ የቀረበው ሀሳብ ውሳኔ እንዲሰጥበት ለድምፅ አቅርበውት ድጋፍ 4 ፣ ታውሞ 486 ፣ ድምፀ ተአቅቦ 1 በመመዝገቡ ሀሳቡ ውድቅ ሆኗል ::

ከዚያም አንቀጽ 12 በረቂቁ ባለበት መልኩ እንዲፀድቅ ለድምፅ ቀርቦ ድጋፍ 486 ፣ ተቃውሞ 1 ፣ ድምፀ ተአቅቦ 3 በመመዝገቡ አንቀጽ 12 እንዳለ በረቂቁ በተቀመጠው መልኩ ፀድቆ ምዕራፍ 2 በአብላጭ ድምፅ መፅደቁን የጉባኤው ሊቀመንበር አመልክተው ለዕለቱ በሕገ መንግሥቱ ረቂቅ ላይ የሚደረገው ውይይት ማብቃቱን ገልጸው ሌላ አስተያየት ካለ ማቅረብ እንደሚቻል አስታውቀዋል ::

በዚህም መሠረት አቶ አሊ አብዶ ከክልል 14 በክልል 14 የሕገ መንግሥት ጉባኤ አባላት ብዛት 23 መሆኑንና ከእነዚህም መካከል 13 ኢሕአዴግን ወክለው የተወዳደሩና ያለፉ መሆናቸውን የቀሩት ደግሞ የግል ተወካዮች እንደሆኑ ገልጸው



J00064



በግል የመጡትም በዲሞክራሲያዊ መንገድ ሀሳባቸው በነፃ በመግለጽና በማራመድ ላይ እንደሆኑ ጠቀመው በጥቂት ሰዎች ምክንያት ስለክልል 14 / አዲስ አበባ / በጅምላ የሚባለውና በተለይም ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ ከክልል 14 ምክር ቤትን እንደ ኢንፎርሜሽን መነሻነት የሚጠቀሙበትን የክልሉን ፕሬዚዳንት ስም ደጋግመው የሚያነሱት በፍፁም ከክልል ምክር ቤቱ ዕውቀት ውጭ መሆኑን ቤቱ እንዲገነዘብላቸው በክልል 14 ምክር ቤት አባልነታቸው አገንዝበዋል ።

በሌላ በኩል አቶ ጀንበሬ ገ/መድህን ከክልል 14 በክልል 14 ከሁለት የፖለቲካ ድርጅቶችና ከግል ተወዳዳሪዎች ለጉባኤው አባልነት እንደተወከሉና የፖለቲካ ድርጅቶችም ኢሕአዴግና እሳቸው የሚወክሉት የጋሞ ዲሞክራሲያዊ ሕብረት /ጋዲሕ / እንደሆነና ከአንድ የፖለቲካ ድርጅት ብቻ ተብሎ የተሰጠው ኢንፎርሜሽን እንዲስተካከል አሳስበዋል ።

በመጨረሻም የጉባኤው ዋና ፀሐፊ አቶ አዲሱ ለገሠ የጉባኤተኞች ስም በተበላ መንገድ እየተጻፈ በየጊዜው ማረምን በመጠየቅ ያለውን ጉባኤተኛ በየጊዜው መኖሩን በትክክል ለማወቅ ስላልተቻለ ይህ እንዳይሆን የክልሉ ወኪሎች የየክልሉን የጉባኤ አባላት ስም ዝርዝር እስከ እነአያታቸው ድረስ በትክክል በመጻፍ ከተቻለም ብሔረሰባቸውን በመጨመር ለጉባኤ አስተናጋጆች ይሰጡ ዘንድ አሳስበው የዕለቱ የጉባኤው ውይይት ከቀኑ 10:50 ሰዓት ተጠናቋል ።

J0006~



ኅዳር 5 ቀን 1987 ዓ.ም ከሚቱ 3:00 ሰዓት በሕገ መንግሥት ጉባኤ አዳራሽ የተጀመረው የሕገ መንግሥት ጉባኤ ስብሰባ የተመራው በጉባኤው ሊቀመንበር በዶ/ር ነጋሶ ጊዳዳ ሲሆን በቅድሚያ የጉባኤው ዋና ፀሐፊ አቶ አዲሱ ለገሠ በዕለቱ የተገኙ የጉባኤ አባላት ብዛት 520 ስለሆነ ምልዓተ ጉባኤው መሟላቱን ባስታወቁት መሠረት ውይይቱ ተጀምሯል ።

የጉባኤው ሊቀመንበር የዕለቱ አጀንዳ ከሰብአዊና ዲሞክራሲያዊ መብት ኮሚቴ የቀረበውን ማብራሪያና የውሳኔ ሀሳብ መሠረት በማድረግ የረቂቅ ሕገ መንግሥቱን ምዕራፍ 3 አንቀጾች ተወያይቶ ማፅደቅ የሚል መሆኑን ገልጸው በቅድሚያ የኮሚቴው ሰብሳቢ ማብራሪያ እንደያቀርቡ ጠይቀዋል ።

በዚህም መሠረት የሰብአዊና ዲሞክራሲያዊ መብት ኮሚቴ ሰብሳቢ ወ/ሮ አረጋሽ አዳነ በረቂቅ ሕገ መንግሥቱ ምዕራፍ 3 የተካተቱ ቢሆንም የሰብአዊና ዲሞክራሲያዊ መብት ኮሚቴ የማያያቸው አንቀጾች የጋብቻ መብት ፣ የግልና የቤተሰብ መብት ፣ የሴቶች መብት ፣ የሕፃናት መብት ፣ የብሔር/ብሔረሰቦችና የሕዝቦች መብት ፣ የንብረት መብት ፣ የኢኮኖሚ ፣ የማህበራዊና የባህል መብት ፣ የልማት መብት ፣ የአካባቢ ደህንነት መብት በሚል የተቀመጡት እንደሆነ ገልጸው እነዚህም በሌሎች ኮሚቴዎች እንደሚታዩ ጠቁመዋል ።

አያይዘውም ኮሚቴው በተቋቋመበት ሥር ያሉትን አንቀጾች ለማየት ጉባኤው በወሰነው መሠረት በተወካዮች ምክር ቤት የፀደቀውን ረቂቅ ሕገ መንግሥት እንደመነሻ እንዲወስደውና ይዘቱን እንዲሁም በአንቀጾቹ አካባቢ ሊነሱ ይችላሉ ተብለው የሚገመቱትን ጥያቄዎችና የተለያዩ ሀሳቦች ፣ አላስፈላጊ የሆኑትንና መስተካከል የሚያስፈልጋቸውን አንቀጾችን ለማየት እንደሞከረ እንዲሁም በአንቀጾቹ ያልተካተቱ ሀሳቦች ካሉ እንዲካተቱ ጥረት ማድረጉን አስታውቀዋል ።

ሰብሳቢው አክለውም የረቂቅ ሕገ መንግሥቱ አጭር ማብራሪያ ፣ የተወካዮች ምክር ቤት በሕገ መንግሥቱ ላይ ስላደረገው ውይይት የተጠናቀረውን ቃለጉባኤ ሰብአዊና ዲሞክራሲያዊ መብቶችን የሚመለከቱ ዓለም አቀፍ ቻርተሮችን እና ጽሑፎችን ኮሚቴው በመነሻነት እንደወሰደ እንዲሁም የሕግ አማካሪዎች እንዳወያየ ገልጸዋል ።

ሰብአዊና ዲሞክራሲያዊ መብት ሲባል ሁለት መሠረታዊ መብቶች እንደሆኑና ሰብአዊ መብት ማለት ሰው ሰው ሆኖ እስካለ ድረስ ከሰውነቱ ተለይተው እንደማይታዩና መብቱም በማንኛው ጊዜ ሊጣስ እና ሊገፈፍ እንደማይችል፣

መብቱን ሊጎናጸፍና ለመተግበር ቅድመ ሁኔታው ሰው መሆን እንደሆነ፣ ዲሞክራሲያዊ መብት ከሰብአዊ መብት የተለየ ሲሆን የሽውም አንድ ሰው ዜጋ በመሆኑ የሚሰጠው መብት መሆኑን ፣ ይህ ብቻም ሳይሆን መብቱን ለመተግበር ከዜግነት በተጨማሪ ሥርዓቱም ዲሞክራሲያዊ መሆን እንዳለበት እና መብቱን ሰው ሁሉ ሊያገኘው እንደማይችል ፣ ለምሳሌ የመምረጥና የመመረጥ መብት ሊያገኝ የሚችለው የሀገሪቱ ዜጋ ብቻ እንደሆነና በአጠቃላይ ሁለቱ መሠረታዊ መብቶች የራሳቸው መነሻ ባህሪይ እና ይዘት ያላቸው መሆኑን አብራርተዋል ፡፡

ከዚያም የኮሚቴው ሰብሳቢ በምዕራፉ የተካተቱን አንቀጾች በተመለከተ በመጀመሪያ አንቀጽ 13ን በንባብ አሰምተው በንዑስ አንቀጽ 1 ላይ የተቀመጠው ፍሬ ሀሳብ የመንግሥት አካላት ለሕገ መንግሥቱ ተገዢ መሆናቸውን፣ የሰብአዊና ዲሞክራሲያዊ መብቶች የማይጣሱ እና የማይደፈሩ መብቶች እንደሆኑና የመንግሥት ሥልጣን ከሕዝቦች መብቶች ጋር በተጣጣመ መንገድ እንዲተገበር የሚገልጽ ፣ መንግሥትም እነዚህን መብቶች የማክበር ብቻ ሳይሆን የማስከበር ግዴታም እንዳለበትና ማንም ሰው አለቃየ አዘዘኝ ነው በሚል ሰበብ እነዚህን መብቶች ሊጥስ እንደማይችል እንዲሁም ክልሎች እነዚህን የሚፃረሩ ሕጎች ማውጣት እንደሌለባቸው ፣ የዳኝነት አካላት ድንጋጌውን የመተርጎምና በሥራ ላይ የማዋል ኃላፊነት እንዳለባቸው የሚያስቀምጥ መሆኑን ፣ ንዑስ አንቀጽ 2 ደግሞ አተረጓጎሙን በተመለከተ ኢትዮጵያ የዓለም አቀፍ ማህበረሰብ አባል በመሆኗ መብቶቹ ከዓለም አቀፍ ስምምነቶች ጋር ተጣጥመው መተርጎም እንዳለባቸው የሚያመለክት መሆኑን ጠቁመው በንዑስ አንቀጽ 1 "ተገዢ መሆን" ከሚለው ቃል ቀጥሎ "የማክበርና የማስከበር ኃላፊነት አለባቸው ፡፡ " የሚል ሐረግ እንዲገባ ማሻሻያ አቅርበዋል ፡፡

ከዚያም አቶ ዓለምሰገድ ገ/አምላክ ከክልል 1 የኮሚቴዎች አካሄድ መጀመሪያ ላይ አስፈላጊ የሆኑትን መንደርደሪያዎችን አጠር አድርገው ካስቀመጡ በኋላ ማሻሻያ ካለ እንዲያቀርቡና ጉባኤው አንቀጽ በአንቀጽ መወያየቱን እንዲቀጥል ያቀረቡት ሀሳብ ተቀባይነት አግኝቷል ፡፡

በዚህም የጉባኤው ሊቀመንበር እስከ አንቀጽ 24 ድረስ ባሉት አንቀጾች የተደረጉ ማሻሻያዎች እንዲቀርቡ ባሳሰቡት መሠረት የኮሚቴው ሰብሳቢ ማሻሻያዎቹን እንደሚከተለው አቅርበዋል ፣

. የአንቀጽ 23 ርዕስ በአንድ ወንጀል ድጋሚ ክስና ቅጣት ስለመከልከል ተብሎ እንዲሻሻል ፣

. አንቀጽ 24 ንዑስ አንቀጽ 2 ...ከሌሎች ዜጎች መብቶች ... የሚለው ተሰርዞ



... ከሌሎች ሰዎች መብቶች ... ተብሎ እንዲሻሻል ፣

. የአንቀጽ 15 ርዕስ "በሕይወት የመኖር መብት " በሚል እንዲሻሻል አሳስበው በተለይ የአንቀጽ 15 ርዕስ ይሻሻልና መሻሻል የለበትም የሚለው ሀሳብ በኮሚቴው እንዳለ ይቀመጥ ወይንስ ይስተካከል የሚለው ልዩነት ፈጥሮ ስለነበር ጉባኤው እንዲወስን አሳስበዋል ፡፡

ቀጥሎም የጉባኤው ሊቀመንበር በማብራሪያውና ከቀረበው መንደርደሪያ በመነሳት የተለየ ሀሳብ አለኝ የሚል ካለ እንዲያቀርብ ባሳሰቡት መሠረት አቶ ሐሰን ኢብራሂም ከክልል 5 አንቀጽ 13 የሚያስተምጠው በምዕራፉ ሥር ያሉትን አንቀጾች አፈጻጸምን በተመለከተ ስለሆነ ጉባኤው አንቀጽ 13 ሌሎች አንቀጾችን ካየ በኋላ እንዲመለከተው ሀሳብ አቅርበዋል ፡፡

ከዚያም አቶ መኩሪያ ታፈሰ ከክልል 14 ለጉባኤው የሥራ ቅልጥፍና አካሄድ ወሳኝ መሆኑን እንደሚያምኑና በእሳቸው አስተሳሰብ ኮሚቴዎች የተቋቋሙት ጉባኤው ያለው ችግር ፣ ሥጋትና ጥያቄዎች መርምረው የመፍትሔ ሀሳብ እንዲያቀርቡና ጉባኤውም በእነዚያ ላይ ተወያይቶ ወደ ድምፅ አሰጣጥ ቢሄድ የተሻለ እንደሆነ ይህም ባለመሆኑ ጉባኤው የሕገ መንግሥቱን መሠረታዊ መርሆዎችን በምዕራፍ 10 ሥር ያሉትን የብሔራዊ ፖሊሲ መርሆዎች መጣጣማቸውን ሳያይ እንደወሰነና ጉባኤው ሊያውቀው የሚፈልገውን ጉዳይ ለምሳሌ የሞት ፍርድ የመሳሰሉት ቢኖሩ ይሻላል ወይስ ባይኖር የሚለውን ኮሚቴው አጥንቶ ጉዳዩ በአንቀጹ እንዲቀመጥ ወይም እንዳይቀመጥ የተደረገበትን ምክንያት ቢያስረዳና ወደ ድምፅ አሰጣጥ ቢኬድ ተገቢ እንደሚመስላቸው አመልክተዋል ፡፡

የጉባኤው ሊቀመንበር የቀረበውን አስተያየት በተመለከተ በሰጡት ምላሽ ጉባኤው በመወያየት ላይ እንጂ ወደ ድምፅ መስጠት እንዳልተሸጋገረ እንዲሁም ጉባኤው ስብሰባውን ግማሽ ግማሽ ቀን ሲያደርግ የነበረው ለኮሚቴዎች ጥናትና ሥራ ጊዜ እንዲኖራቸውና የጉባኤ አባላት ጥያቄዎቻቸውን ለየኮሚቴዎቹ እንዲሰጡ ታስቦ እንደሆነና አሁንም ሌሎች ኮሚቴዎች ሪፖርታቸውን እስኪያቀርቡ ድረስ ጊዜ ስላለ ሀሳብ ወይም ጥያቄ ያለቸው የጉባኤ አባላት በጉዳያቸው መሠረት ለሚመለከታቸው ኮሚቴዎች ማቅረብ እንደሚችሉ አስታውቀዋል ፡፡

ቀጥሎም አቶ መሀሙድ ድሪር ከክልል 5 የሰብአዊና ዲሞክራሲያዊ መብት ኮሚቴ በሰጠው ማብራሪያ ላይ የሰብአዊ መብት ሰው የሰው ልጅ በመሆኑ የሚያገኘው መብት እንደሆነና ዲሞክራሲያዊ መብቶች ደግሞ ለሰው ልጅ ሁሉ የሚሰጡ መብቶች እንዳልሆኑ የተብራራ መሆኑን ጠቁመው መብት ሰጪው ማን እንደሆነ ጠይቀው በኢትዮጵያ በአሁኑ ሥርዓት ዲሞክራሲያዊ መብቶች በትግል

የተገኙ እንደሆነና መብት ሰጪና መብት ተቀባይ ሊኖር እንደማይገባ አመልክተዋል ።

የቀረበው ሀሳብ ላይም የማብራሪያው መንፈስ የኮሚቴው ሰብሳቢ ሲያስረዱም ዲሞክራሲያዊ መብት ለዜጎች የሚሰጥ መብት ነው ሲባል መብቱን የሚሰጥ አካል አለ ማለት ሳይሆን ሊኖር የማይችልበት ጊዜ ሊከሰት እንደሚችልና መብቱ የሚከበረውም ሥርዓቱ ዲሞክራሲያዊ ሲሆን እንደሆነ ፣ ይህም በሕዝብ ትግል ሊረጋገጥ እንደሚችል ለመግለጽ መሆኑን አስረድተዋል ።

ከዚያም ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ ከክልል 14 በአንቀጽ 13 ንዑስ አንቀጽ 2 ላይ ኢትዮጵያ ከገባችባቸው ዓለም አቀፍ ግዴታዎች ጋር ይህ አንቀጽ እንደሚታይ በመስፈሩ ማወቅና ማስተያየት እንዲቻል ሕጎቹ ምን ምን እንደሆኑ በአጭሩ እንዲዘረዘሩ ስለጠየቁ ዶክሜንቶቹን ከተወካዮች ምክር ቤት ሆነ ከሌሎች የመንግሥት አካላት ማግኘት እንደሚቻል የጉባኤው ሰብሳቢ ገልጸው በምዕራፍ 3 ውስጥ የሰብአዊ መብቶችን በተመለከተ ያሉት አንቀጾች የዓለም አቀፍ የሰብአዊ መብቶች ኮንቬንሽንኖች የሚመለከቱ መሆናቸውን ጠቁመዋል ።

ቀጥሎም አቶ መኩሪያ ታፈሰ ከክልል 14 በአንቀጽ 13 ንዑስ አንቀጽ 2 ላይ "ኢትዮጵያ ከተቀበለቻቸው ዓለም አቀፍ ሰነዶችና መርሆዎች ጋር በተጣጣመ መልኩ ይተረጎማል ። " ሲባል በዓለም አቀፍ ሰነዶች ውስጥ ያሉ አንቀጾች እዚህ ካሉት አንቀጾች ጋር በትርጉም ባይጣጣሙ ፍርድ ቤቶች የትኛውን የበላይ ሕግ አድርገው እንደሚወስዱት እንዲብራራላቸው ጠይቀዋል ።

የኮሚቴው ሰብሳቢ ኢትዮጵያ ያፀደቀቻቸው ዓለም አቀፍ ስምምነቶች እዚህ ካሉት አንቀጾች ጋር የተሳሰረ ባህሪይና የተጣጣመ ይዘት ያላቸው እንጂ የተለያዩ አለመሆናቸውን ፣ የአንቀጹ መንፈስም በተግባር ተጣጥመው እንዲተረጎሙ የሚያስቀምጥ እንደሆነና ኢትዮጵያም ስምምነቶቹን የተቀበለችው ካሏትና ከሚኖሯት ሕጎች ጋር ያለመጣጣም ችግር እንደማይከሰት እምነት ስላለ ለተቀመጡት አንቀጾች ተገገር መሆን እንዳለባቸው አብራርተዋል ።

በሌላ በኩል አቶ ሙሉጌታ ገ/ሕይወት ከክልል 1 አንቀጽ 13 ንዑስ አንቀጽ 1 በማንኛውም ደረጃ የሚገኝ የፌዴራል መንግሥትና የክልል ሕግ አውጪ ፣ ሕግ አስፈጻሚና የዳኝነት አካላት መሠረታዊ መብቶችንና ነፃነቶችን የማክበርና የማስከበር ግዴታ እንዳለባቸው የሚገልጽ እንደሆነ ጠቁመው በተለይ ባለፉት ሥርዓቶች የሀገር መከላከያ ፣ የፖሊስና የደህንነት ተቋማት ባላቸው የጠበቀ የእዝ





ሰንሰለት በአለቃ ታዝዤ ነው በማለት ከሕግ በላይ በመሆናቸው የሰብአዊና ዲሞክራሲያዊ መብቶችን ይጥሱ እንደነበር አመልክተዋል ።

አክለውም እነዚህ ሁኔታዎች እንዳይቀጥሉ በተለየ ሁኔታ በሕገ መንግሥቱ ማስገባት እንደሚያስፈልግ ጠቁመው አንቀጽ 13 1 ... የፌዴራል መንግሥትና የክልል ሕግ አውጪ" ከሚለው ቀጥሎ «የሀገር መከላከያ ፣ የፖሊስ እና የደህንነት ተቋማት» የሚል ሐረግ እንዲታከልበት ሀሳብ አቅርበዋል ።

ከዚያም አቶ ሁሴን መሐመድ ከክልል 4 ከተፈጻሚነት አተረጓጎም ስለሚቀድም በአንቀጽ 13 ንዑስ አንቀጽ 2 ላይ የተቀመጠው የአተረጓጎም ጉዳይ ስለሆነ ንዑስ አንቀጽ 1 እንዲሆንና በንዑስ አንቀጽ 1 ላይ የተቀመጠው ደግሞ የአፈጻጸም ጉዳይ ስለሆነ ንዑስ አንቀጽ 2 ሆኖ እንዲቀመጥ ሀሳብ አቅርበዋል ።

ቀጥሎም አቶ ዚያድ ዳውድ ከክልል 5 በአንቀጽ 13 ንዑስ አንቀጽ 1 ላይ የተቀመጠው ለሰብአዊና ዲሞክራሲያዊ መብቶች መከበር ዋስትና የሚሰጥ ባለመሆኑ ዋስትና በሚሰጥ መልኩ ንዑስ አንቀጹ እንዲቀመጥ ጠቁመው በንዑስ አንቀጥ 2 ላይ ያለውም ግልጽ ስላልሆነ በዝርዝር በግልጽ እንዲቀመጥ አሳስበዋል ።

አስከትለውም አቶ አብዱራዛቅ መሐመድ ከክልል 14 በአንቀጽ 13 ንዑስ አንቀጽ 2 ውስጥ የተካተቱት ዓለም አቀፍ ስምምነቶች እ.አ.አ. በዲሴምበር 10/1948 ዓ.ም የፀደቀው የተባበሩት መንግሥታት የሰብአዊ መብቶች ቻርተር ፣ በ1952 የፀደቀው የዓለም የሠራተኛ ማህበር ስምምነቶች ፣ በ1966 የፀደቀው የዓለም አቀፍ የሲቪልና የፖለቲካ መብቶች ስምምነት በመሆናቸው አንቀጹ በአጠቃላይ ኮሚቴው ካቀረበው ማሻሻያ ጋር እንደሚቀበሉት አስታውቀዋል ።

በሌላ በኩል አንቀጽ 13 ግዴታዎችንም ጭምር ያካተተ እንደሆነ አቶ ተመስገን ማሞ ከክልል 14 ገልጸው ርዕሱ መሠረታዊ መብቶች ፣ ነፃነቶችና ግዴታዎች በሚል እንዲሻሻል ሀሳብ አቅርበዋል ።

ከዚያም የጉባኤው ዋና ፀሐፊ የቀረቡትን የማሻሻያ ሀሳቦች አጠቃልለው ካቀረቡ በኋላ ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል አቶ አህመድ ሀሰን ጉባኤው ከክልል 5 አቶ ሀሰን ኢብራሂም በአንቀጽ 13 የተቀመጠው ምዕራፍ 3 አጠቃልሉ የያዘ ስለሆነ በመጨረሻ እንየው በማለት ያነሱትን ጥያቄ አስፈላጊ መሆኑን አምነውበት እንድተዉት ፣ በአቶ ሙሉጌታ ገ/ሕይወት ከክልል 1 በአንቀጽ 13 ንዑስ አንቀጽ 1 ላይ የፖሊስ ፣ የመከላከያና የደህንነት ተቋማት ይታከል በማለት ያቀረቡትን ሀሳብ በሕገ መንግሥቱ በዝርዝር ሊቀረጽ እንደማይችል ፣ ሆኖም ሕግ አስፈጻሚ ተብሎ ስለተቀመጠ አፋኝ ተቋማትንና ቢሮክራሲውን ማለት መሆኑ ግልጽ እንደሆነ ፣

በንዑስ አንቀጽ 2 ላይ በዝርዝር ማስቀመጥ እንደማያስፈልግ ምክንያቱም ሀገራችን ብዙ ያልፈረመቻቸው ስምምነቶች እንዳሉና ወደፊት እንደምትፈርም ፣ ለምሳሌ ብዙ ያልፈረመቻቸው ስምምነት መፈረሟን ፣ ይህ በቅርብ ጊዜ የጦር ምርኮኞች ሰብአዊ አያያዝ ስምምነት መፈረሟን ፣ ይህ በቅርብ ጊዜ የጦር ምርኮኞች ሰብአዊ አያያዝ ስምምነት እንደነበር ፣ የሕፃናት መብት ከመፈረሙ በፊት በትግሉ ጊዜ ተግባራዊ ሲሆን እንደነበር ፣ የሕፃናት መብት ኮንቬንሽንን ተግባራዊ ለማድረግ የኢኮኖሚ አቅሙ ባይኖረንም እንደተፈረመ ገልጸው በአጠቃላይ አንቀጹን ኮሚቴው ካቀረበው ማሻሻያ ጋር ጉባኤው እንዲቀበለው አሳስበዋል ::

ከዚያም የኮሚቴው ሰብሳቢ ወ/ሮ አረጋሽ አዳነ አንቀጽ 13ን በኋላ እንየው ለሚለው በመሠረታዊ ሁኔታው ልዩነት እስከሌለ ድረስ ችግር እንደማያመጣ ፣ የአንቀጽ 13 ንዑሳን አንቀጾች ቦታ መቀያየር የሚያመጣው መሠረታዊ ለውጥ እንደሌለ ፣ ኢትዮጵያ ያፀደቀቻቸው ዓለም አቀፍ ስምምነቶች ዝርዝር ሕጎች እንደ ማለት ከአጀንዳ ውጭ እንደሆነ ከአብራሩ በኋላ ጉባኤው በቂ ውይይት ስላደረገበት ወደ ውሳኔ እንሂድ የሚለው ለድምፅ ቀርቦ በአብላጫ ድምፅ ተደግፏል ::

በዚህም መሠረት በአንቀጽ 13 ንዑስ አንቀጽ 1 «በማንኛው ደረጃ የሚገኙ የፌዴራል መንግሥትና የክልል ሕግ አውጪ ፣ ሕግ አስፈጻሚና የዳኝነት አካላት በዚህ ምዕራፍ የተካተቱትን ድንጋጌዎች የማክበርና የማስከበር ኃላፊነትና ግዴታ አለባቸው :: » በሚል ተሻሽሎ እንዲቀመጥ ኮሚቴው ያቀረበውን የውሳኔ ሀሳብ ለድምፅ ቀርቦ ድጋፍ 514 ፣ ተቃውሞ 4 ፣ ድምፀ ተአቅቦ 3 በመመዝገቡ ንዑስ አንቀጹ በተሻሻለው መልኩ ተቀባይነት አግኝቶ አንቀጽ 13 በአጠቃላይ ኮሚቴው ካቀረበው ማሻሻያ ጋር በቀረበው መልኩ እንዲቀመጥ ተወስኗል ::

ጉባኤው ከሻይ ዕረፍት በኋላ ውይይቱ በአንቀጽ 14 ላይ የቀጠለ ሲሆን በመጀመሪያ ሰብሳቢ አንቀጹን በንባብ አሰምተው በይዘቱ ፣ በቃላቱ ወይም በአቀማመጡ ላይ ሀሳብ እንዲሰጥበት ጠይቀዋል ::

ከዚያም አቶ አህመዲን ኢብራሂም ከክልል 4 አንቀጽ 14 በግልጽና በማያሻማ መልኩ የተቀመጠ እንደሆነ ጠቁመው ጉባኤው እንዳለ እንዲቀበለው የውሳኔ ሀሳብ አቅርበዋል :: ውሳኔ ሀሳቡም በጉባኤው ተቀባይነት ስላገኘና ተቃውሞም ባለመኖሩ አንቀጹ ለድምፅ ቀርቦ ድጋፍ 518 ፣ ድምፀ ተአቅቦ 1 ያለምንም ተቃውሞ አንቀጹ በረቂቁ በተቀመጠው መልኩ እንዲቀመጥ ተወስኗል ::

ቀጥሎም ሰብሳቢው አንቀጽ 15ን በንባብ ካሰሙ በኋላ በአንቀጹ ላይ ሀሳብ እንዲሰጥበት ባሳሰቡት መሠረት አቶ ሙሉጌታ ገ/ሕይወት ከክልል 1 አንቀጽ 15 ፣ 16 ፣ 17 አንቀጽ 14ን በበለጠ የሚያብራሩ በመሆናቸው የአንቀጽ 14 ንዑሳን አንቀጾች ሆነው እንዲጠቃለሉ ሀሳብ አቅርበዋል ::



በሌላ በኩል አቶ ቴዎድሮስ ባከፋ ከክልል 3 ደግሞ "በሕግ በተደነገገ ከባድ የወንጀል ቅጣት ካልሆነ በስተቀር ሕይወቱን አያጣም ::" የሚለው አባባል ከአንቀጽ 13 ንዑስ አንቀጽ 2 ላይ በዓለም አቀፍ ስምምነቶች ውስጥ የተካተተው በሕይወት የመኖር መብትና በቀረበው አንቀጽ በከባድ ወንጀል ሕይወት የማጣት ቅጣት እንዴት ሊጣጣም እንደሚችል ጠይቀዋል ::

አቶ መሀሙድ ድሪር ከክልል 5 አቶ ቴዎድሮስ ባከፋ ባነሱት ሀሳብ ላይ የተቀመጠውን በአፅንኦት የሚያመለክት እንጂ የሚቃረን አለመሆኑን ምክንያቱም ማንም ሰው በሕይወት የመኖር መብቱ የተጠበቀ እንደሆነና ያለፍርድ እንደማይሞት እንዲሁም ሕገ መንግሥቱ ለወንጀለኞች ከለላ እንደማይሰጥ ለማስቀመጥ መሆኑን አስረድተዋል ::

ከዚያም አቶ መሐመድ ሼክ አህመድ እና አቶ እጅጉ ገ/ሚካኤል ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል አንቀጹ ትክክለኛ በመሆኑ በቀረበው መልኩ እንዳለ እንዲቀመጥ ሀሳብ አቅርበዋል ::

በሌላ በኩል የኮሚቴው ሰብሳቢ ወ/ሮ አረጋሽ አዳነ ደግሞ አንቀጽ 15 ፣ 16 ፣ 17 አንድ ላይ ይሁኑ ተብሎ ለቀረበው ሀሳብ በአንቀጾቹ የተካተቱት መሠረታዊ መብቶች በመሆናቸው ጎላ ብለው የየራሳቸውን አንቀጾች መያዝ እንዳለባቸውና ከዚህ በመለስ ቅርጹን የሕገ መንግሥት ቅርጽ ኮሚቴ ሊያየው እንደሚችል አስረድተው የአንቀጽ 15 ርዕስ "በሕይወት የመኖር መብት" ተብሎ በኮሚቴው አብላጫ ድምፅ እንዲሻሻል ሀሳብ መቅረቡን ገልጸዋል ::

ቀጥሎም የጉባኤው ዋና ፀሐፊ አቶ አዲሱ ለገሠ "የመኖር" መጨመሩ የሚያመጣው ልዩነት እንደሌለ ገልጸው ኮሚቴው ይጨመር ካለ በአንቀጽ 14 ርዕስ "በሕይወት የመኖር መብት" ተብሎ እንዲጨመር ሀሳብ ማቅረብ እንደነበረበት አስገንዝበዋል ::

ከዚያም የጉባኤው ሊቀመንበር በአንቀጹ ላይ መሠረታዊ የሀሳብ ልዩነት ባለመኖሩ ድምፅ እንዲሰጥበት ያቀረቡትን ሀሳብ ጉባኤው ያለ ምንም ተቃውሞ ስለደገፈው የአንቀጽ 15 ርዕስና አንቀጹ እንዳለ ይቀመጥ የሚለው የውሳኔ ሀሳብ ለድምፅ አቅርበውት ድጋፍ 516 ፣ ድምፀተአቅቦ 4 በመመዝገቡ ያለ ምንም ተቃውሞ የአንቀጹ ርዕስና አንቀጹ እንዳለ እንዲቀመጥ ተወስኗል ::

ቀጥሎም ጉባኤው ውይይቱን በአንቀጽ 16 ላይ የቀጠለ ሲሆን አንቀጹን በንባብ ከተሰማ በኋላ የማሻሻያ ሀሳብ እንዲሰጥበት ተጠይቋል ::

በዚህም መሠረት ፕሮፌሰር ጀማል አብዱልቃድር ከክልል 4 አንቀጽ 16 "ማንኛውም ሰው በሕግ በተደነገገ የወንጀል ቅጣት ካልሆነ በስተቀር የአካል ጉዳት አይደርስበትም ::" የሚል ዐረፍተ ነገር እንዲታከልበት ሀሳብ አቅርበዋል ::

በተጨማሪም አቶ ተስፋዬ ፊቻላ ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል "ማንኛው ሰው የአካል ጉዳት እንዳይደርስበት ራሱን የመጠበቅ እና በመንግሥት የመጠበቅ መብት አለው ::" የሚል ማሻሻያ አቅርበዋል ::

በሌላ በኩል አቶ መሀሙድ ድሪር ከክልል 5 ደግሞ አንቀጽ 16 እንደ ግርፋት /ቶርች/ ዓይነት ጉዳቶችን እንደሚከላከል ጠቅሰው በአገራችን ከተለያዩ ብሔር ብሔረሰቦች ባህል የተነሳ የሚፈጸሙ የአካል ጉዳቶች እንዳሉ ለምሳሌም ያህል በሶማሌ ክልል ብልትን የመተርተር ጎጂ ባህል እንዳለ ጠቅሰው በዚህ ዓይነት የሚከሰቱትን ባህላዊ የአካል ጉዳቶችን ለማስወገድ በሕገ መንግሥቱ እንዲካተት አሳስበዋል ::

አያይዘውም ይህ በአንቀጽ 16 "ማንኛው ሰው ከባህላዊና የእምነት አካል ጉዳት የመጠበቅ መብት አለው ::" የሚል ዐረፍተ ነገር እንዲታከልበት በሕገ መንግሥቱ መግባት የለበትም ከተባለም ያቀረቡት ባህላዊ የአካል ጉዳት መነሻው ቢቃለጉባኤ እንዲመዘገብላቸው ጠይቀዋል ::

በሌላ በኩልም አቶ አብዱልከሪም አህመድ ከክልል 5 የአንቀጹ መንፈስ ማንኛው ሰው በአካሉ ላይ ጉዳት እንዳይደርስበት የመከላከል መብት አለው በሚል እንደተረጎሙት ገልጸው ራስን በመከላከል በሌላ አካል ላይ የሚያደርሰው ጉዳት ተጠያቂ አይሆንም የሚል እንዲጨመርበት ሀሳብ አቅርበዋል ::

የኮሚቴው ሰብሳቢ ወ/ሮ አረጋሽ አዳነ ለቀረቡት ሀሳቦች በሰጡት ምላሽ በሕግ ከተደነገገ የአካል ጉዳት ሊደርስ ይችላል ለሚለው የአንቀጹ መንፈስ ሰው ሆኖ ጥፋተኛ መሆኑ ተረጋግጦ በጥፋቱ አንፃር የሚገባውን ቅጣት እስኪያገኝ ድረስ በአካሉ ላይ ምንም ዓይነት ጉዳት ሊደርስበት አይችልም የሚል በመሆኑ ይህን መንፈስ የሚያንፀባርቀው አንቀጽ እንዳለ ቢቀመጥ የተሻለ እንደሆነ ፣ራሱን የመጠበቅ መብት አለው ለተባለውም የመንግሥት ሥልጣን ከሕዝብ ነፃነትና መብት አንፃር ስለሚመሠረት የመጠበቅ ኃላፊነቱን ለማስቀመጥ እንጂ በግሉ የመጠበቅ መብቱን ማስቀመጡ አሳስፈላጊ እንደሆነ ገልጸው ስለጎጂ ባህሎች የተነሳው በሌላ አንቀጽ የተካተተ መሆኑን አብራርተዋል ::



ቀጥሎም አቶ አህመዲን ኢብራሂም ከክልል 4 አንቀጽ 16 ከላይ በአንቀጽ 14 15 ላይ እንደተጠቀሱት ሁሉ የማይሸራረፍ ሰብአዊ መብት መሆኑን ፣ ጥፋተኛ ሰው እንኳን ቢሆን አካሉ ሊጎድል እንደማይችል ፣ ይህ ለወንጀለኛ በር ሊከፍት ይችላል የሚል ሥጋት ቢኖርም አጥፊ በጥፋቱ ይቀጣል እንጂ በአካሉ ላይ ጉዳት ሊደረስበት እንደማይገባ ለማስቀመጥ ታስቦ እንደሆነ ገልጸው ጎጂ ባህሎችን በተመለከተም አንቀጽ 9 በተቀመጠው መሠረት ተቀባይነት እንደሌላቸውና ባህላዊ ውብት ከባህላዊ ጉዳት ተለይቶ መታየት እንዳለበት አስታውቀው አንቀጹ እንዳለ እንዲፀድቅ አሳስበዋል ::

ከዚያም አቶ መኩሪያ ታፈሰ ከክልል 14 አንቀጽ 16 "ማናኛውም ሰው በአካሉ ላይ በቀጥታም ሆነ በተዘዋዋሪ ጉዳት እንዳይደርስበት የመጠበቅ መብት አለው ::" በሚል ቢሻሻል የሰውን መንፈስ በማሰጨነቅ የአካል ጉዳት የሚያደርሱትን ድርጊቶች ሊገቱ እንደሚችሉ ገልጸዋል ::

ለዚህም አቶ ግርማ ብሩ ከክልል 4 በተዘዋዋሪ መንገድ የስነልቦናዊ ተፅዕኖ በማድረግ የአካል ጉዳት እንዳይደርስ የአንቀጹ መንፈስ ስለሚያንፀባርቅ አንቀጹ እንደለ እንዲቀመጥ ሀሳብ አቅርበዋል ::

ከዚያም ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ ከክልል 14 በሴቶች ላይ ብዙ በደል እንደሚፈጸምና በሃይማኖት ሰበብ ሰይጣን ይዟታል ከተባለ በፀሎት መዳን ሲገባ በአለንጋ እንደሚገረፉ ቀሪው ሀሳባቸውን ለሴቶች ጉዳይ ኮሚቴ አቀርባለሁ ስላሉ ማቅረብ እንደሚችሉ ተፈቅዶላቸዋል ::

ቀጥሎም አቶ ዓለምሰገድ ገ/አምላክ ከክልል 1 በአንቀጽ 16 ላይ "በቀጥታም ሆነ በተዘዋዋሪ" የሚል ሐረግ ይግባ ለተባለው የሥነልቦናዊ ጉዳት ስለሚያስከትል በአንቀጽ 18 ንዑስ አንቀጽ 1 ላይ የተቀመጠ መሆኑን ገልጸው አቶ መሀሙድ ድሪር ያቀረቡትን ሀሳብ መነሻ እንደሚቀበሉት ፣ ሆኖም አንቀጽ 16 በባህልና እምነት የተነሳ የሚፈፀሙ የአካል ጉድለቶች ይፈቀዳል እስካልተባለ ድረስ የተከለከለ እንደሆነ አስገንዝበው ጉዳዩም በቃለጉባኤ ተካትቶ አንቀጹ ግን ምንም ሳይታከልበት እንዳለ እንዲቀመጥ አሳስበዋል ::

ፕሮፌሰር ጀማል አብዱልቃድር ከክልል 4 ስላነሱት ጉዳይ የተደረገው ገለጻ ያረካቸው መሆኑን ጠቁመው ሀሳባቸውን መሳባቸውን አስተውቀዋል ::

ከዚያም የጉባኤው ሊቀመንበር በአንቀጽ 16 ላይ በቂ ውይይት እንደተደረገበት ገልጸው ውይይቱ ቆሞ በአንቀጹ ላይ ድምፅ እንዲሰጥበት ያቀረቡት ሀሳብ በሙሉ ድምጽ ተደግፏል ::

በዚህም መሠረት አንቀጽ 16 በረቂት ባለው መልኩ እንዳለ እንዲቀመጥ ለድምፅ ቀርቦ በሙሉ ድምፅ ተደግፎ ፀድቋል ::

ጉባኤው ውይይቱን በአንቀጽ 17 ላይ የቀጠለ ሲሆን የጉባኤው ሊቀመንበር አንቀጹን በንባብ ካሰሙ በኋላ ማሻሻያ ወይም አስተያየት ካለ ማቅረብ እንደሚቻል አስታውቀዋል ::

በዚሁ መሠረትም የሰብአዊና ዲሞክራሲያዊ መብቶች ኮሚቴ ሰብሳቢ ወ/ሮ አረጋሽ አዳነ አንቀጽ 17 ንዑስ አንቀጽ 1 መሠረታዊ መብት በመሆኑ "ማንኛው ሰው" ከሚለው ቀጥሎ "ወንድ ወይም ሴት" የሚል ሐረግ እንዲታከልበት ሀሳብ አቅርበዋል ::

በሌላም በኩል አቶ ደበበ አበራ ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል "ማንኛው ሰው" የሚለው በንዑስ አንቀጹ እንዳለ ከሆነ የውጭ ዜጋም ቢሆን ወደ ኢትዮጵያ ገብቶ ነፃነቴ ይጠበቅልኝ ሊል ስለሚችል ንዑስ አንቀጹ "ማንኛውም ኢትዮጵያዊ/ት" ተብሎ እንዲሻሻል ሀሳብ አቅርበዋል ::

ቀጥሎም አንድ የጉባኤው አባል ንዑስ አንቀጽ 2 "ማንኛው ሰው ክስ ቀርቦበት ሳይፈረድበት በጥርጣሬ አይታሰርም ::" በሚል እንዲሻሻል ሀሳብ ሲያቀርቡ ፣ ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ ከክልል 14 ደግሞ አንድ ሰው ስለተከሰሰ ብቻ መታሰር ስለሌለበት "ማንኛውም ሰው ፍርድ ቤት ቀርቦ ሳይከሰስና ሳይከራከር አይታሰርም" በሚል እንዲሻሻል የሚል ሀሳብ ሰንዝረዋል ::

በሌላ በኩል ወ/ሮ ራህመትና አቶ ታደሰ ካሳ ከክልል 3 እንደዚሁም አቶ ኢዲሱ ለገሠ አንቀጽ 17 ንዑስ አንቀጽ 1 የነፃነት መብትን የሚደነግግ እንደሆነና መብቱም መሠረታዊ ስለሆነ ንዑስ አንቀጹ በሁለቱም ፆታዎች አገላለጽና የሴቶችን የነፃነት መብትም እንዲያስረግጥ "ማንኛው ሰው" ከሚለው ቀጥሎ "ወንድ ወይም ሴት ነፃነቱን/ቷን አያጣም /አይታጣም :: " በሚል እንዲቀመጥ አሳስበዋል ::

ከዚያም አቶ ወንድሙ ቱሮ ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል የፆታ አገላለጽ ጉዳይ በአንቀጽ 7 ላይ የተወሰነ እንደሆነ ገልጸው አንቀጽ 17 ንዑስ አንቀጽ 1 በረቂቁ ባለበት መልኩ እንዳለ እንዲቀመጥ ሀሳብ አቅርበዋል ::

ቀጥሎም አቶ አባይ ፀሐዬ ከክልል 1 በተለያዩ የጉባኤው አባላት በአንቀጽ 17 ላይ የቀረቡትን ሀሳቦች በተመለከተ በሰጡት አስተያየት አንድ ሰው በፍርድ ቤት ጥፋተኛነቱ ተረጋግጦ ፍርድ እስኪሰጠው ድረስ መታሰር የለበትም የተባለው



በአፈጻጸም አስቸጋሪ እንደሆነ ፣ ለምሳሌ አንድ ሰው ወንጀል ሲፈጽም እጅ ከፍንጅ እንኳን ቢያዝ ፍርድ ቤት አልወሰነበትም በሚል እንዲለቀቅና ሌላ ወንጀል እንዲሠራ ወይም መረጃዎችን እንዲያጠፋ እንደሚያደርግ ፣ ይህ እንዳይሆን አንድ ሰው በወንጀል ሲያዝ ፖሊስ ምርመራውን በ24 ሰዓት ካላጠናቀቀ ተጨማሪ ጊዜ እንዲሰጠው ፍርድ ቤቱን እንደሚጠይቅ ፣ በተጨማሪ ጊዜም ጉዳዩን አጣርቶ ለፍርድ ቤት እንዲያቀርብ ፣ ሆኖም አንድ ጉዳዩ በመጣራት ላይ ያለ ሰው ጥፋተኛ መሆኑን በፍርድ ቤት እስኪረጋገጥበት ድረስ እንደ ጥፋተኛ እንደማይቆጠር አብራርተዋል ::

አያይዘውም ከባድ ወንጀል የፈጸመ ወይም ሰው የገደለ ሰው ጠፍቶ በፍለጋ ከተያዘ በኋላ ፍርድ ቤት እንዲታሰር ሳይፈርድበት አይታሰርም የሚለው ወንጀልን የሚያስፋፋ ስለሆነ ፍርድ ቤት ትዕዛዝ ወይም ፍርድ ሳይሰጥ አይታሰርም ከሚል አኳያ መታየት እንዳለበት አስገንዝበዋል ::

አክለውም በአንቀጽ 17 በወንድ ፆታ የተገለው ሁሉ ለሴቶችም እንደሚሆን ቢወሰንም ነፃነት መሠረታዊ መብት ስለሆነና የአንስታይ ፆታ አገላለጽ ቢታከልበት የሴቶችን የነፃነት መብት ስለሚያስረግጥ ኮሚቴው ባቀረበው መልኩ የማሻሻያ ሀሳብ መሠረት እንዲቀመጥ አሳስበዋል ::

ከዚያም ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ ከክልል 14 አቶ አባይ ፀሐዬ ሀሳባቸውን በስህተት እንደጠቀሱባቸው ጠቅሰው ፖሊስ ለምርመራ ወንጀል የፈጸመን ሰው አይሰር እንዳላሉ ፣ እሳቸው ያሉት ላልተወሰነ ጊዜ ያለፍርድ ሰው መታሰር የለበትም የሚለውን እንደነበር ገልጸዋል ::

ቀጥሎም ጉባኤው በአንቀጽ 17 ላይ በቂ ውይይት ያደረገ በመሆኑ አንቀጹ ድምፅ እንዲሰጥበት የጉባኤው ሊቀመንበር ባሳሰቡት መሠረት በአብላጫ ድምፅ ድጋፍ አግኝቷል ::

በዚህም መሠረት አንቀጽ 17 አንቀጽ 1 "በሕግ ከተደነገገው ሥርዓት ውጭ ማንኛውም ሰው ወንድ ወይም ሴት ነፃነቱን/ቷን አያጣም /አይታጣም ::" በሚል ተሻሽሎ አንቀጽ 17 በአጠቃላይ እንዲፀድቅ ለድምፅ ቀርቦ ድጋፍ 509 ፣ ተቃውሞ 3 ፣ ድምፀ ተአቅቦ 4 በመመዝገቡ አንቀጽ 17 ከነማሻሻያው ፀድቆ ጉባኤው ለምሳ 7:15 ተነስቷል ::

ጉባኤው ከሰዓት በኋላ በ9:10 ውይይቱን ከመቀጠሉ በፊት የጉባኤው ዋና ፀሐፊ አቶ አዲሱ ለገሠ በጉባኤው አዳራሽ የተገኙት የጉባኤ አባላት ብዛት ከ500 በላይ ስለሆነ ውይይቱ መጀመር እንደሚቻል ከገለጹ በኋላ የጉባኤው ሊቀመንበር ዶ/ር ነጋሶ ጊዳዳ የሰብአዊና ዲሞክራሲያዊ መብቶች ኮሚቴ "ኢሰብአዊ አያያዝን ስለመከልከሉ " በሚል ርዕስ በተቀመጠው አንቀጽ 18 ላይ የሚለውጥ ቃልም ሆነ ሐረግ እንዲሁም ሀሳብ እንዳሌለ ጠቁመው ቤቱ አንቀጹን እንዳለ እንዲቀበለው ሀሳብ ማቅረቡን አመልክተው ከቤቱ የተለየ ሀሳብ ካለ እንዲቀርብ ጠይቀዋል ::

በዚህም መሠረት አቶ ዳንኤል በላይነህ ከክልል 14 ማንም ሰው በፍላጎቱ እንጂ በግዴታ ግልጋሎት መስጠት የሌለበት ሲሆን በቅርብ ጊዜ ግን ማኅበረሰቡ ተገዶ የተሰማራበት ሁኔታ መኖሩን ለምሳሌ ባለፈው ሥርዓት ወጣቱ ያለፍላጎቱ ብሔራዊ ውትድርና መዝዱን ጠቅሰው በአንቀጽ 18 ንዑስ አንቀጽ 4/ሐ/ ላይ የተጠቀሰውም የማስገደድ ሁኔታ ስላለው እንዲወጣ የሚል ሀሳብ ያቀረቡ ሲሆን አቶ አዳሙ ደገፉ ከክልል 14 እና አቶ ደቶራ ዳራ ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል ደግሞ በንዑስ አንቀጽ /ለ/ ላይ የተቀመጠው እንዲብራራላቸው ጠይቀዋል ::

ቀጥሉም አቶ ገዛሙ ቀልቦ ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል ከጋሙ ብሔረሰብ በንዑስ አንቀጽ 2 "ማንኛው ሰው በባርነት ወይም በግዴታ አገልጋይነት ሊያዝ አይችልም..." የሚለው ሲታይ በፈቃደኝነት በተለያየ ክፍያ አገልግሎት መስጠት እንደማያግድ ሁሉ በግዴታ ካለሆነ በፈቃደኝነት ባርነትም ይቻላል የሚል እንድምታ እንዳይኖረው ለማድረግ ማንኛው ሰው በባርነት መያዝ የለበትም ተብሎ ለብቻው እንዲጠቀስ ሀሳብ አቅርበዋል ::

በማስከተልም አቶ እጅጉ ገ/ሚካኤል ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል ከሲዳማ ብሔረሰብ መንግሥት የሕዝብን ደህንነት የመምራትና የመጠበቅ ኃላፊነቱን ለመወጣት ለምሳሌ የእሳተ ገሞራ አደጋ ቢከሰት ሰዎቹን ከዚያ አካባቢ ለማሸሽ በንዑስ አንቀጽ 4/ሐ/ የተጠቀሰው አስፈላጊ መሆኑን ፣ እንዲሁም ንዑስ አንቀጽ 4/ለ/ አንዳንድ ሃይማኖቶች በጦር ሜዳ የሚገድልህንም ሰው እንኳን ቢሆን አትግደል የሚል መመሪያ ስላላቸው ምናልባት በአገር ወረራና በመሳሰሉት በማይዘምቱበት ጊዜ ዘመቻውን የሚያካክስ ሌላ ምትክ ሥራ ይሰጣቸዋል ለማለት ስለሆነ ተገቢ እንደሆነ ፣ ስለዚህም በአንቀጽ 18 የሰፈሩት ኢሰብአዊ አያያዝን የሚከለከሉ ስለሆነ በአሉበት መልኩ እንዲፀድቁ ሃሳብ አውቅርበዋል ::

ቀጥሉም የሰብአዊና ዲሞክራሲያዊ መብቶች ኮሚቴ ሰብሳቢ ወ/ሮ አረጋሽ አዳነ አንቀጽ 18ን በተመለከተ ከቤቱ የተነሱ ጉዳዮችን አስመልክተው በሰጡት ማብራሪያ አጠቃላይ የኅብረተሰቡ ደህንነት የሚነዱ ችግሮች ሲከሰቱ የኅብረተሰቡ ችግርና



የግለሰብ መብት ተሳስሮ የሚሄድ እንደሚሆን ፣ ስለዚህ ጠቅላላ ኅብረተሰቡን የሚጎዳ ችግር ሲከሰት የአስቸኳይ ጊዜ አዋጅ ሲታወጅ ሁሉም ለአዋጁ ተገዥ መሆን እንዳለበት ፣ በመሆኑም በንዑስ አንቀጽ 4/ሐ/ ላይ የተጠቀሰው ግለሰቡንም ሆነ ኅብረተሰቡን የማዳን ተልዕኮ የያዘ ቢሆንም አስገዳጅነት ስላለው ይውጣ መባሉ ትክክል እንዳልሆነ ጠቅሰዋል ::

በተጨማሪም ንዑስ አንቀጽ 4/ሐ/ በወታደራዊ አገልግሎት ለምሳሌ ባዕድ ወራሪ መጥቶ የአስቸኳይ ጊዜ አዋጅ ሲታወጅ እንደ አእምሮ በሽተኛ የመሳሰለ ግላዊ ችግር ያለባቸው የግድ ወደ ብሔራዊ ውትድርና የማይገቡ ስለሚሆን ሌላ ምትክ ሥራ ይሠራሉ የሚል መንፈስ እንደለሌው ኮሚቴው መገንዘቡን ፣ በንዑስ አንቀጽ 2 " ማንኛውም ሰው በባርነት ወይም በግዴታ አገልጋይነት ሊያዝ አይቻልም ..." የሚለው ሰውን በመሸጥና በመለወጥ እንደ ባርያ አድርጎ መያዝና በግዴታ አገልጋይ ማድረግን በመከልከል ሰብአዊ አያያዝ እንዲጠበቅ ለማድረግ መሆኑን ፣ ከዚህም አንፃር በክፍያ ግልጋሎት ማግኘትን ወይም አገልጋዩ ክፍያ ቢኖረውም ለመኖር ባልፈለገ ጊዜ በተለያዩ ጫናዎች እንዲቆይ ማድረግን ፣ እንዲሁም ሕፃናትን መስረቅ የመሳሰሉትን ለመከላከል በመሆኑ በባርነት ወይም በግዴታ የሚሉት ቃላት በአንድነት አስፈላጊ መሆናቸውን አብራርተዋል ::

ከዚያም የጉባኤው ዋና ፀሐፊ አቶ አዲሱ ለገሠ በንዑስ አንቀጹ ላይ " በባርነት ወይም በግዴታ" የሚለው ማንኛውም ሰው በባርነት እንዲሁም በግዴታ አገልጋይነት ሊያዝ እንደማይደይችል ለይቶ የሚያመለክት እንጂ ባርነትን ከግዴታ ጋር በማያያዝ ባርነት በፈቃደኝነት ሊከናወን ይችላል ማለት እንዳልሆነ ያስገነዘቡ ሲሆን በሌላ በኩል አቶ ደተራ ዳራሞ ጉዳዩ ግልጽ ስለሆነላቸው ሀሳባቸውን እንደሳቡ አስታውቀዋል ::

በማስከተልም አቶ ጀንበሬ ገ/መድህን ከክልል 14 በንዑስ 4/ለ/ እንደተጠቀሰው ወታደራዊ አገልግሎት ለመስጠት ሕሊናው የማይፈቅድለት ሰው ሌላ ምትክ ሥራ በግዴታ ከተሰጠው በንዑስ አንቀጽ 3 ላይ ማንኛውም ሰው በኃይል ተገዶ ወይም ግዴታን ለማሟላት ማንኛውንም ሥራ እንዲሠራ ማድረግ የተከለከለ ሰው የሚለውን አይጥስም ወይ ? የሚል ጥያቄ ስላቀረቡ ንዑስ አንቀጽ 4 የሚያሳየው በንዑስ አንቀጽ 3 የተጠቀሰውን መብት እንዳለ ሆኖ ነገር ግን አስፈላጊ ሲሆን ልዩ ሁኔታዎች እንደሚፈጠሩና ልዩ ሁኔታዎችም ምን እንደሆኑ መሆኑን ሰብሳቢው ምላሽ ሰጥተዋል ::

ቀጥሎም አቶ ዳንኤል በላይነህ ከክልል 14 ማንኛውም ኢትዮጵያዊ የሚያደርጋቸው ነገሮች ሁሉ በፈቃደኝነት እንጂ በግፊት መሆን ስለሌለበት የሚመሠረተው መንግሥት በእርስ በርስ ጦርነት ወቅት ሳይሆን የውጭ ወራሪ በሚመጣበት ጊዜ የአስቸኳይ ጊዜ አዋጅ አውጥቶ ማንኛውንም ዜጋ ማሰለፍ ስለሚችል ንዑስ አንቀጽ 4 /ሐ/ የማህበረሰቡን ሕይወትና ደህንነት የሚያሰጋ የውጭ ወራሪ በሚያጋጥምበት ጊዜ የአስቸኳይ ጊዜ አገልግሎት ሁኔታ በማካተት እንዲሻሻል በዚህ መልክ ካልተሻሻለ ግን እንዳለ እንዲሰረዝ የሚል ሀሳብ አቅርበዋል ::

በሌላ በኩል ደግሞ አቶ ዳንኤል ደሴ ከክልል 4 የማኅበረሰቡን ሕይወት ወይም ደህንነት አደጋ ላይ የሚጥለው ከጦርነት ጋር ብቻ ማያያዝ እንደማያስፈልግና ለምሳሌ በሕንድ እንደተከሰተው የወረርሽኝ በሽታ ዓይነት ሊፈጠር እንደሚችል እንዲሁም የፀጥታ ሁኔታ መታሰብ እንዳለበት ፣ ንዑስ አንቀጽ 4 /ለ/ ደግሞ በተለያየ ምክንያት ወታደራዊ አገልግሎት መስጠት የማይችል በሚቻለው ሌላ የሲቪል መስክ በማገልገል የዜግነት ግዴታውን እንዲወጣ መሆኑን ጠቁመዋል ::

ቀጥሎም አቶ ዓለምሰገድ ገ/አምላክ ከክልል 1 የአቶ ዳንኤል በላይነህ ሥጋት የአስቸኳይ ጊዜ አዋጅ ለእርስ በርስ ጦርነት መግሪያ እንዳይሆን ሲሆን የአስቸኳይ ጊዜ አዋጅ መቼ እንደሚታወጅ አንቀጽ 95 ንዑስ አንቀጽ 1 ላይ የተጠቀሰ ስለሆነ ቤቱ እንዲገነዘበው ኢንፎርሜሽን ሰጥተዋል ::

በመጨረሻም የሰብአዊና ዲሞክራሲያዊ መብቶች ኮሚቴ ባቀረበው መሠረት አንቀጽ 18 ባለው መልክ ወይንስ ንዑስ አንቀጽ 4 /ለ/ እና /ሐ/ ይውጡ የሚሉ አማራጭ የውሳኔ ሀሳቦች ለድምፅ ቀርበው የሰብአዊና ዲሞክራሲያዊ መብቶች ኮሚቴ ባቀረበው መሠረት አንቀጽ 18 ባለው መልኩ የሚለው ፣ ድጋፍ 521 ፣ ተቃውሞ 5 ፣ ያለምንም ድምፀ ተአቅቦ አንቀጹ እንዳለ ፀድቋል ::

ቀጥሎም የጉባኤው ሊቀመንበር የሰብአዊና ዲሞክራሲያዊ መብቶች ኮሚቴ አንቀጽ 19 በቀረበው መልኩ ተቀባይነት እንዲያገኝ ሀሳብ ማቅረቡን ገልጸው ተቃውሞ ወይም የሚጨመር ሀሳብ ካለ እንዲቀርብ ቤቱን ጠይቀዋል ::

በዚህም መሠረት አቶ ሸምሰዲን አህመድ ከክልል 5 በአንቀጽ 19 ንዑስ አንቀጽ 4 ላይ "... አስፈላጊ በሆነ መጠን ..." እና "... በተቻለ ፍጥነት" የሚሉት ሐረጎች የጊዜ ገደብን ስለማያመለክቱ አንደ ሰው በምርመራ ስም ፍርድ ቤት ሳይቀርብ በጥበቃ ሥር የሚቆይበትን ጊዜ በማራዘም ሰብአዊ መብቱን ሊገፋ ስለሚችል የጊዜ ገደቡ በሕግ እንደሚደነገግ መጠቆም አለበት የሚል ሀሳብ አቅርበዋል ::



ቀጥሎም አቶ አብዱልራዛቅ መሐመድ ከክልል 14 አንድ የተያዘ ሰው የሚታወቅ አድራሻ ካለው መያዙን ለዘመዶቹ ለማሳወቅ እንዲቻል "የተያዙ ሰዎች መያዛቸውን ወዲያውኑ የቅርብ ዘመዶቻቸው እንዲያውቁላቸው የመጠየቅ መብት አላቸው :: " የሚል ድንጋጌ ራሱን ችሎ በንዑስ አንቀጽ 3 "የተያዙ ሰዎች ላለመናገር መብት አላቸው :: በሚገባቸው ቋንቋ የሚሰጡት ማንኛውም ቃል ለፍርድ ቤቱ ማስረጃ መሆኑን ሊነገራቸው ይገባል :: " ቢባል መሠረተ ሀሳቡን ሳይቀይር ድግግሞሽን በማስወገድ ግልጽነት እንደሚኖረው አሳስበዋል ::

አስከትሎም አቶ አህመዲን ኢብራሂም ከክልል 4 በአንቀጽ 19 ንዑስ አንቀጽ 5 ላይ "... በማስገደድ የተገኘ ማስረጃ ተቀባይነት አይኖረውም :: " የሚለው ሲታይ ለምሳሌ በአንድ የነፍስ ግድያ ወንጀል ጉዳዩ ካልታወቀና ምስክር ወይም ማስረጃ ከሌለ አንድ ተጠርጣሪ ሰው ተይዞ ተገዶ በመምራት የገደለበትን መሣሪያ ሲያሳይ በንዑስ አንቀጽ 5 በተጠቀሰው መሠረት ማስረጃው ውድቅ ስለሚሆን ያስገደደው የሚጠየቅበትን መንገድ ቢቀየስና የተገኘው ማስረጃ ግን ሌላ ማስረጃ ከሌለ ውድቅ እንዳይሆን የንዑስ አንቀጹ ሁለተኛ ዐረፍተ ነገር "...በማስገደድ የተገኘ ማስረጃን በሚመለከት አስገዳጁ በሕግ ይጠየቃል:: " በሚል እንዲሻሻል አስተያየት ሰጥተዋል ::

በሌላ በኩል አቶ ተስፋዬ ፊቻላ ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል ከሲዳማ ብሔረሰብ በአቶ አህመዲን ኢብራሂም የቀረበው የአንቀጽ 19 ንዑስ አንቀጽ 5 ሁለተኛው ዓረፍተ ነገር ማሻሻያ በቀጥታ ባይሆንም በተዘዋዋሪ ማስገደድን ሕጋዊ ማድረግን ስለሚሆን "በማስገደድ የተገኘ ማስረጃ ተቀባይነት አይኖረውም ::" የሚለው እንዲወጣና ቀሪው የንዑስ አንቀጹ ድንጋጌ በቂ መሆኑን ጠቁመዋል ::

ከዚያም የጉባኤው ሊቀመንበር አንቀጽ 19 ንዑስ አንቀጽ 3 የቋንቋ ግልጽነት ጉዳይ የሕገ መንግሥት ቅርጽ ኮሚቴ ሊመለከተው እንደሚችል ጠቁመው በአንቀጹ ሥር የተነሱ ሌሎች ጉዳዮችን በተመለከተ የሰብአዊና ዲሞክራሲያዊ መብቶች ኮሚቴ ተወያይቶባቸው ከሆነ እንዲገልጽ አሳስበዋል ::

በዚህም መሠረት የኮሚቴው ሰብሳቢ ወ/ሮ አረጋሽ አዳነ ቤቱ ያነሳቸው ሀሳቦች ሁሉ በኮሚቴው ታይተዋል ለማለት እንደማይቻል እና በአንዳንድ ጉዳዮች ላይ የራሳቸውን አስተያየት እንደሚገልጹ ጠቅሰው ጉባኤው በአንቀጽ 18 እንዳፀደቀው ማንም ሰው እስር ቤት ቢገባ ኢሰብአዊ በሆነ መንገድ መያዝ እንደሌለበት በመሆኑም ቃል እንዲሰጥ በሚጠየቅበት ጊዜ ቃሌን አልሰጥም እስከማለት እንደሚችልና ማስረጃ ለማግኘት ሲባል የማስገደድ ሁኔታ ከተፈጸመ ግን የሕዝቦችና

እንደሚጣስ ፣ ጉባኤው ያፀደቀው ድንጋጌ የግለሰቦች ሰብአዊ መብት እንደሚጣስ ፣ ስለዚህ በንዑስ አንቀጽ 5 ላይ "... በማስገደድ የተገኘ ማስረጃ እንደማይተገበር ፣ ስለዚህ በንዑስ አንቀጽ 5 ላይ "... በማስገደድ የተገኘ ማስረጃ እንደማይተገበር ፣ ስለዚህ በንዑስ አንቀጽ 5 ላይ" የሚለውን ኮሚቴው እንዳለ እንደተቀበለው ተቀባይነት አይኖረውም ፡፡ " የሚለውን ኮሚቴው እንዳለ እንደተቀበለው ተቀባይነት አይኖረውም ፡፡ " የሚለውን ኮሚቴው እንዳለ እንደተቀበለው ተቀባይነት አይኖረውም ፡፡ " አስታውቀዋል ፡፡

አያይዘውም ማንኛውም ባለሥልጣን ሰብአዊ መብቶችን ማክበርና ማስከበር እንዳለበት ጉባኤው ቀደም ሲል በመወሰኑ ባለሥልጣኑ ባለው ኃላፊነት ፍርድ ቤት እንዳለበት ጉባኤው ቀደም ሲል በመወሰኑ ባለሥልጣኑ ባለው ኃላፊነት ፍርድ ቤት የቀረበውን ሰው በጥበቃ ሥር የሚቆይበትንና ምርመራ የሚያካሂድበትን ጊዜ ከተጨባጭ ሁኔታው ጋር በማገናዘብ በቶሎ ያስፈጽምለታል በሚል መንፈስ ካልታለፈ በስተቀር በንዑስ አንቀጽ 4 ላይ የተወሰነ ቀናትም ሆነ ወራት የጊዜ ገደብ ማስቀመጥ ለሥራ አስቸጋሪ እንደሚሆን ፣ ስለዚህ ፍርድ ቤት ምን ያህል የጊዜ ገደብ ይፍቀድ የሚለውን ጉዳይ ኮሚቴው እንዳልተመለከተው ፣ በተጨማሪም የተያዘ ሰው መያዙን ለዘመዶቹ የማሳወቅ ሁኔታ ጉባኤው ካፀደቃቸው መሠረታዊ መብቶች አኳያ ተያይዞ ተግባራዊ የሚሆን እንጂ ለብቻው ተነጥሎ ድንጋጌ የሚያስፈልገው እንዳልሆነ ገልጸዋል ፡፡

በሌላ በኩል ደግሞ አቶ አዳሙ ደገፉ ከክልል 14 ከዚህ ቀደም በነበረው አሠራር ፍርድ ቤት ቀርቦ በሚደረግ ጊዜያዊ ቀጠሮ ለብዙ ጊዜ መቆየት እንደነበር ለምሳሌ አንድ ሰው በወንጀለኛነት ተከሶ አውራጃ ፍርድ ቤት ቀርቦ ጊዜያዊ ቀጠሮ የተሰጠ ሲሆን ሰውየው አስታዋሽ ወይም ዘመድ በማጣቱ 3 ዓመት ከ8 ወር ታስሮ በመቆት ለፍርድ ቤት መቅረቡን ፣ በመሆኑም አጠር ባለ መልኩ የጊዜ ገደብ እንዲደረግ የሚል ሀሳብ አቅርበዋል ፡፡

ቀጥሎም አቶ መሀሙድ ድሪር ከክልል 5 ቤተሰብ የተያዘን ሰው መያዙን ማወቅና መጠየቅን በተመለከተ በአንቀጽ 21 የተካተተ በመሆኑ በአንቀጽ 19 ንዑስ አንቀጽ 2 ሆኖ እንዲገባ አቶ አብዱራዛቅ መሐመድ ያቀረቡት ሀሳብ እንደማያስፈልግ አመልክተዋል ፡፡

ከዚያም አቶ ሙሉጌታ ገ/ሕይወት ከክልል 1 የአንድ እስረኛ በጥበቃ ሥር መቆየትንና ምርመራ የሚካሄድበትን የጊዜ ገደብን በተመለከተ በንዑስ አንቀጽ 4 የተጠቀሰው ችግር ሲከሰተ በንዑስ አንቀጽ 6 መሠረት በዋስ ለመለቀቅ ጥያቄ ማቅረብ እንደሚቻል ፣ በዋስ ለመለቀቅ የሚያስችሉ ሕጎች ደግሞ በወንጀለኛ መቅጫ ሕግ ላይ በዝርዝር እንደተቀመጡ ስለሚጠቁም ንዑስ አንቀጽ 4 ባለው መልኩ ቢሆን ይሻላል የሚል ሀሳብ አቅርበዋል ፡፡



በማስከተልም አቶ ዓለምሰገድ ሃአምላክ ከክልል 1 ንዑስ አንቀጽ 4 ፍትሕ እንዳይጓደል ሁኔታው የሚጠይቅ ከሆነ ፍርድ ቤቱ የተያዘው ሰው በጥበቃ ሥር እንዲቆይ ለማዘዝ ወይም ምርመራ ለማካሄድ ተጨማሪ ጊዜ ሲጠይቅ አስፈላጊ በሆነ መጠን ብቻ ሊፈቅድ ይችላል ፡፡ ስለሚል በሰው ወንጀለኛ ሰብአዊ መብት እንደማይጣስና የሚፈቀደው ጊዜ መረጃውን ለማጠናቀር የሚያስፈልግ የጊዜ መጠን ብቻ እንደሚሆን አስፈላጊ ከሆነው ጊዜ በላይ የታሰረ በሕግ ለመጠየቅ እንደሚችል፣ በርግጥ ጉዳዩ በወንጀለኛ መቅጫ ሕግም እንደሚታይ ፣ ወንጀል የማጣራት ሂደት የሚያስፈልገው ጊዜ እንደወንጀሉ ሁኔታ ሊለያይ ስለሚችል በሕገ መንግሥቱ የጊዜ ገደብ ከተቀመጠ በአፈጻጸም ወቅት በጣም አስቸጋሪ ሁኔታ ሊፈጥር ይችላል የሚል አስተያየት አቅርበዋል ፡፡

አያይዘውም በአንዳንድ አገሮች አሠራር ወንጀለኛ እንዳያመልጥ ሲባል በማስገደድ የሚገኝ ማስረጃን በሙቀበል አስገዳጅን እካል እንደሚቀጡ ፣ በመሆኑም ይህ አሠራር የማስገደድን ተግባር ሙሉ በሙሉ የማያስተር እንደሆነ ፣ በንዑስ አንቀጽ 5 "... በማስገደድ የተገኘ ማስረጃ ተቀባይነት አይኖረውም ፡፡" የሚለው ግን የማስገደድን ተግባር በሙሉ የሚያስወግድ እንደሆነ ፣ ያለው ሥጋት መረጃን በመደበቅ ወንጀል እንዳይስፋፋና ማስገደድ ተፈቅዶ ሰብአዊ መብት እንዳይጣስ መሆኑን ፣ ስለዚህ አንቀጹ ለወንጀለኛ ማምለጫ ቀዳዳ የሚከፍት ቢሆንም ማስገደድ ከተፈቀደ ወንጀለኛ ብቻ ሳይሆን ወንጀለኛ ተብሎ የተገመተው ሰውም ሊገደድ ስለሚችል ሰብአዊ መብት እንዳይጣስ በመገንዘብ ሰብአዊ መብትን ያስቀደመ በመሆኑ እንዳለ ቢቀመጥ የተሻለ እንደሆነ አመልክተዋል ፡፡

ቀጥሎም አቶ ሸምሰዲን አህመድ ከክልል 5 በአንቀጽ 19 ንዑስ አንቀጽ 5 የተገለጸው አስፈላጊ ባልሆነ ምክንያት ቀጠሮ ተራዝሞ የሰው ሰብአዊ መብት እንዳይጣስ እና ዕውነት የሚገኝበትን መንገድ ላለመከላከል የሚሠሩትን ለማጣጣም ከማብራሪያውና ከጽሑፉ እንደተገነዘቡት፣ ፍርድ ቤቶች ከፍተኛ ኃላፊነት ወስደው የሚያስከብሩ መሆኑን ፣ ስለዚህ አንድ ሰው በጥበቃ ሥር የሚቆይበትና ምርመራ የሚካሄድበት የጊዜ ገደብ በቀናትና በወራት ባይወሰንም በሕግ ይወሰናል እንዲባል አቅርበውት የነበረው ሀሳብ ወደ ዝርዝር ጉዳዮች ሊያመራ ስለሚችል ሀሳባቸውን ማንሳታቸውን አስታውቀዋል ፡፡

እንዲሁም አቶ አብዱራዛቅ መሐመድ ከክልል 14 እና አቶ አህመዲን ኢብራሂም ከክልል 4 ሀሳባቸው መሳባቸውን የጉባኤው ሊመንበር ጠቅሰው ጉባኤው በአንቀጽ 19 ላይ በቂ ውይይት ስላካሄደ ቤቱ ወደ ውሳኔ ሀሳብ እንዲሸጋገር ያቀረቡትን ሀሳብ ከአንድ የጉባኤ አባል በስተቀር በተቀሩት አባላት በሙሉ ተደግፏ ፡፡

በመጨረሻም አንቀጽ 19 በረቂቅ ሕገ መንግሥቱ ባለበት መልኩ ለማፅደቅ ለድምፅ ቀርቦ ድጋፍ 518 ፣ 1 ተቃውሞ ፣ ያለምንም ድምፀ ተአቅቦ ፀድቋል ::

ጉባኤው ከሻይ ዕረፍት በኋላ ውይይቱን የቀጠለው በአንቀጽ 20 ላይ ሲሆን የሰብአዊና ዲሞክራሲያዊ መብቶች ኮሚቴ አንቀጹ በረቂቁ ላይ በቀረበው መልኩ እንዲፀድቅ የውሳኔ ሀሳብ ማቅረቡን ሰብሳቢው ገልጸው ከቤቱ በአንቀጹ ላይ የተለየ አስተያየት ካለ ማቅረብ እንደሚቻል አመልክተዋል ::

በዚህም መሠረት አቶ ዑመር አብዱስታረ ክክልል 13 ንዑስ አንቀጽ 2 ላይ "ክሱ በቂ በሆነ ዝርዝር እንዲነገራቸው እና ክሱ በጽሑፍ የማግኘት መብት አላቸው :: " በሚለው መጀመሪያ ላይ "በሚገባቸው ወይም መረዳት በሚችሉት ቋንቋ " የሚል እንዲጨመርበት የሚል ሀሳብ አቅርበዋል ::

በሌላ በኩልም አቶ መኩሪያ ታፈሰ ከክልል 14 በአሁኑ ወቅት የኢትዮጵያ ሕዝብ የሰብአዊ መብት ችግር ከቀደም የተሻለ ቢሆንም ሕዝቡ ነፃነቱን አግኝቶ ወደ ልማትና ብልጽግና እንዲራመድ ሙሉ በሙሉ በማያጠራጥር ሁኔታ ሰብአዊና ዲሞክራሲያዊ መብት ሊኖረው ስለሚገባ ንዑስ አንቀጽ 3 ላይ "... መብት አላቸው የሚለው ማሠሪያ ሐረግ "... መብት ተረጋግጦላቸዋል ::" ተብሎ እንዲሻሻል ፣ እንዲሁም ንዑስ አንቀጽ 5 ላይ "... ከመንግሥት ጥበቃ የማግኘት መብት አላቸው::" የሚለው ተገቢ ቢሆንም የአንዱ መብት መጠበቅ የሌላው መብት እንዳይነካ ምናልባት የመንግሥት ያልሆነ ጠበቃ ከቆመላቸው ወጪውን የመክፈል ሁኔታ እንዲካተትበት ጠይቀዋል ::

ከዚያም አቶ አዳሙ ደገፉ ከክልል 14 ፍርድ ቤት በዝግ ችሎት የሚያያቸው ጉዳዮች ተቀምጠው ሰውን በመጉዳት የሕዝብን መብት ሊጥስ ስለሚችል በንዑስ አንቀጽ 1 ላይ "... ሆኖም የተከራካሪዎችን የግል ሕይወት ፣ የሕዝብን የሞራል ሁኔታና የሀገሪቱን ደህንነት ለመጠበቅ ሲባል ብቻ ክርክሩ በዝግ ችሎት ሊታይ ይችላል :: " የሚለው እንዲሰረዝ ሀሳብ ያቀረቡ ሲሆን አቶ መሐመድ ጣሀር ከክልል 5 ደግሞ አንድ ሰው ተከሶ ምስክሮች ሲቀርቡ ምስክሮችን የመቃወምና እኔን የሚቃረኑ ናቸው የማለት መብቱ የተረጋገጠ መሆን እንዳለበት ጠቁመዋል ::

ቀጥሎም አቶ ግርማ ከበደ ከክልል 3 በረቂቅ ሕገ መንግሥት ማብራሪያ ላይ እንደተጠቀሰው በዝግ ችሎት የሚታዩ ጉዳዮች ማህበራዊ ብጥብጥን ያስከትላሉ ተብለው የሚገመቱ ፣ በኢትዮጵያና በሌሎች አገሮች መካከል ብጥብጥ ሊያስከትሉ ይችላሉ የሚባሉ ፣ የአገሪቱ ወታደራዊ ሚስጥሮችና ሰነዶች የመሳሰሉት እንደሆኑ ፣ የተጠቀሱት በዝግ ችሎት የሚታዩት የአገርን ደህንነት ወይም ሉዓላዊነት ከማስ ጠበቅ አኳያ መሆኑን ፣ ከእነዚህም ሌላ በዝግ ችሎት የሚታዩት አሳስፈላጊ የሆኑ



የሃይማኖት ግጭቶች ሊያመጡ ይችላሉ ተብለው የሚገመቱ እንደዝሙትና የመሳሰሉት የአንድን ግለሰብ ወይም ቤተሰብ ስብዕና ሊነኩ ይችላሉ ተብለው የሚገመቱ ጉዳዮች እንጂ ማንኛው ጉዳይ እንዳልሆነ አስረድተዋል ::

አያይዘውም ወንጀለኛ ግለሰቦች በአቃቤ ሕግ ወይም በፖሊስ ቢከሰሱም አቅም የሌላቸው ሰዎች ሲኖሩ መንግሥት ጠበቃ እንደሚያቆምላቸው ንዑስ አንቀጽ 5 እንደሚያመለክት ፣ ከዚህ ባሻገር ግን የመንግሥት ጠበቃን አልፈልግም ብሎ ሌላ ጠበቃ ለሚያቆመው ግለሰብ መንግሥት ወጪውን እንዲሸፍንለት ተብሎ እንደ መብት በሕገ መንግሥቱ እንደማይካተት ጠቁመዋል ::

በተጨማሪም በዓለም አቀፍ ድንጋጌ አንቀጽ 11 ላይ ማንኛው የተከሰሰ ሰው ሁሉ ወንጀለኛ እንዳልሆነ እንደሚጠቁምና ከክሱ ጀምሮ ፍርድ ቤት እስከሚወሰንበት ድረስ ያለውን ድንጋጌው በግልጽ ስላስቀመጠ በንዑስ አንቀጽ 3 ያለውን ማሻሻያ እንደማያስፈልግና ኢሰብአዊ ድርጊት እንዲፈጸም በር የማይከፍት ትክክለኛ አገላለጽ እንደሆነ አመልክተዋል ::

በማስከተልም አቶ ታደሰ ግርሚሶ ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል ያለፉት ሥርዓቶች ለሕዝብ የሚጠቅም ድንጋጌ በማውጣት በተግባር ግን ሰዎችን ወይም ወንጀለኞችን ኢሰብአዊ በሆነ መልክ ይይዙ እንደነበር ፣ አሁን ግን የተከሰሱ ሰዎችን መብት በሚመለከት በተጨባጭ በዝርዝር ያስቀመጣቸው ሁኔታዎች እንዳሉና ካለፉት ሥርዓቶች ጋር በማያያዝ ጥርጣሬ ውስጥ መግባት እንደማያስፈልግ በመሆኑም ወደፊት ከሚመሠረተው ዲሞክራሲያዊ ሥርዓት ተግባራዊነት አኳያ በማገናዘብ ካለፉት ሥርዓቶች የተለየ መሆኑን መመልከት እንደሚገባ ፣ ስለዚህ በንዑስ አንቀጽ 1 ላይ የተቀመጠውም ወደፊት በተጨባጭ ለመጠቀም የሚያስችለን የሚዘረዝር በመሆኑ መውጣት እንደሌለበትና ሌሎችም ንዑስ አንቀጾች በተገቢው መልክ የተቀመጡ መሆኑን ጠቅሰው ቤቱ እንዲቀበላቸው ሀሳብ አቅርበዋል ::

ከዚያም አቶ ዑመር አብዱስታር ከክልል 13 በንዑስ አንቀጽ 2 በተጨማሪነት እንዲካተት ያቀረቡት ሀሳብ አቶ ታሪኩ ዕጌ በንዑስ አንቀጽ 7 የተጠቀሰ መሆኑን ሲጠቁሙ ዶ/ር አብዱልመጂድ ሁሴን ደግሞ በአንቀጽ 19 ንዑስ አንቀጽ 1 ላይ የተከተተ መሆኑን አስገንዝበዋል ::

በሌላ በኩል አቶ ሀሰን አሊ ከክልል 4 ደግሞ የተከሰሱ ሰዎች በሚገባቸው ቋንቋ ትርጉም ለመስጠት ከተፈለገ የትርጉም ሕጋዊነት እንደሚኖሳ በመሆኑም ትርጉሙ ሕጋዊ ለመሆን በሕግ ፊት ተቀባይነት ሊኖረው እንደሚገባ እንዲሁም በአገሪቱ ውስጥ ላሉ የተለያዩ በርካታ ብሔረሰቦች ለፍርድ በቀረቡ ቁጥር በቃል ከማስተርጎም ውጭ የጽሑፍ ትርጉም ይካሄዳል ከተባለ በአፈጻጸም ወቅት በጣም

እንደሚያስቸግር ፣ ስለዚህ የቃል ትርጉም እንጂ የጽሑፍ ትርጉም እንደሚያሰጥ በንዑስ አንቀጹ መካተት እንደሌለበት ሀሳብ አቅርበዋል ::

ቀጥሉም አቶ ዑመር አብዱሰታር ከክልል 13 የተሰጡትን አስተያየቶች መሠረት በማድረግ ባቀረቡት ሀሳብ ንዑስ አንቀጽ 2 ከስን በጽሑፍ መስጠት ሲሆን ንዑስ አንቀጽ 7 ግን የፍርድ ቤት ውስጥ ክርክር መሆኑን ፣ በአንቀጽ 19 ንዑስ አንቀጽ 1 ደግሞ« ... በሚገባቸው ቋንቋ እንዲነገራቸው መብት አላቸው ::» ስለሚል በጽሑፍ ከመስጠት የተለየ መሆኑን ፣ አቶ ሀሰን አሊ የሰጡት ማብራሪያ ደግሞ ንዑስ አንቀጽ 73 የሚመለከት ሲሆን እርሳቸው ያቀረቡት ሀሳብ ግን ንዑስ አንቀጽ 23 በሚመለከት መሆኑን አስታውቀዋል ::

ከዚያም የጉባኤው ሊቀመንበር ጉዳዩ የመብት ጥያቄ ሳይሆን ቴክኒካል ጥያቄ መሆኑንና ከቴክኒክ አኳያም በጣም እንሚያስቸግር ፣ በመሆኑም በውጭ አገር ባለው አሠራር በፍርድ ቤት አስተርጓሚ ሊቆም እንደሚችል ነገር ግን ክሱ በጽሑፍ ተከሳሹ ወደሚገባው ቋንቋ ተተርጉሞ እንደማይሰጥ አመልክተዋል ::

በመጨረሻም በጉዳዩ ላይ ቤቱ በበቂ ሁኔታ መወያየቱን በመስማማት ወደውሳኔ ሀሳብ ማተላለፍ የተሸጋገረ ሲሆን አንቀጽ 20 እንዳለ በረቂቁ ባለበት መልኩ እንዲቀመጥ ለድምፅ ቀርቦ ድጋፍ 504 ፣ ተቃውሞ 1 ፣ ድምፀ ተአቅቦ 1 በመመዝገቡ አንቀጹ በረቂቁ ባለበት መልኩ ይቀመጥ የሚለው ተቀባይነት አግኝቷል ::

ቀጥሉም የጉባኤው ሊቀመንበር የሰብአዊና ዲሞክራሲያዊ መብት ኮሚቴ አንቀጽ 21 በረቂቁ በተቀመጠው መልኩ እንዲፀድቅ ሀሳብ ማቅረቡን ገልጸው ከቤቱ በአንቀጹ ላይ አስተያየት ካለ ማቅርብ እንደሚቻል አስታውቀዋል ::

በዚህም መሠረት አቶ ደስታ ቁናሳ ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል ቀደም ሲል የፍርድ ዓይነቶች በሚል ርዕስ ሥር የእስራት ዓይነቶች እንደነበሩና በዚህ ሁኔታ ሲታይ ፅኑ እስራት የተፈረደባቸውና ፅኑ እስራት ያልሆኑ ተብለው እንደሚታወቁ ፣ ፅኑ እስራት የተፈረደበት አንዳንድ መብቶች ለምሳሌ የጡረታ መብት ይገፈፍ እንደነበር ፣ አሁን በቀረበው ሕገ መንግሥት ግን ፅኑ እስራት የሚል ስለሌለ ወደፊት በሚወጣው ሕግ የሚካተት ከሆነ የመንግሥት ሠራተኛ ፅኑ እስራት የሚያስፈርድበት ወንጀል ሠርቶ በመታሰር ጡረታውም እንዳይታገድና የሚያስተዳድራቸው ቤተሰቦች ችግር ላይ እንዳይወድቁ ለማድረግ በምን መልኩ መከላከያ እንደሚኖረው ጠይቀዋል ::



ለዚህም አቶ ዳንኤል ደሲ ከክልል 4 በሰጡት ምላሽ በአንቀጽ 21 የተጠቀሰው በጥበቃ ሥር ያሉና በፍርድ የታሠሩ ሰዎችን መብት የሚመለከት ሲሆን የተነሳው ጥያቄ ግን የሥራ ዋስትናን ማግኘት እንደሆነና ከአንቀጹ ጋር እንዳልተያያዘ እንዲሁም በአገሪቱ ዲሞክራሲያዊ ሥርዓት የቀረበውን ችግር የሚፈጥር ድንጋጌ እንደማያወጣ ጠቅሰዋል ::

በተጨማሪም አቶ ደበበ አበራ ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል አንቀጽ 21 በጥበቃ ሥርና በእስር ላይ ያለ ሰብአዊ መብቶቹ ተከብረው መያዝ እንዳለበት የሚያመለክት ሲሆን የሥራ ዋስትናን በተመለከተ ግን የሠራተኞች ማህበራዊ ጉዳዮችን በሚያመለክቱ ሌሎች አንቀጾች ያካተቷቸው ስላሉ ከአንቀጽ 21 ጋር ተያያዥነት ስለሌለው አንቀጹን እንዳለ ቤቱ እንዲቀበለው ሀሳብ አቅርበዋል ::

ከዚያም በአንቀጹ ላይ በቂ ውይይት ስለተደረገበት ወደውሳኔ መስጠቱ እንዲኬድ አብዛኛው የጉባኤ አባላት በመደገፋቸው አንቀጽ 21 እንዳለ እንዲፀድቅ ለድምፅ ቀርቦ በሙሉ ድምፅ ተደግፎ ፀድቋል ::

ቀጥሉም የጉባኤው ሊቀመንበር የሰብአዊና ዲሞክራሲያዊ መብት ኮሚቴ አንቀጽ 22 በረቂቁ ባለው መልኩ እንዲፀድቅ ሀሳብ ያቀረበ መሆኑን ጠቅሰው በአንቀጹ ላይ ከቤቱ አስተያየት ካለ ማቅረብ እንደሚቻል ገልጸዋል ::

በዚህም መሠረት አቶ መኩሪያ ታፈሰ ከክልል 14 የአንቀጽ 22 ርዕስ «የወንጀል ሕግ ወደኋላ ተመልሶ የማይሠራ ስለመሆኑ» ስለሚል በወንጀለኛ መቅጫ ያልተከለከለውን ነገር ሁሉ ማንም ሰው መሥራት ይችል ወይም አይችል እንደሆነ እንዲብራራ የጠየቁ ሲሆን በዚህ ወቅት የሰብአዊና ዲሞክራሲያዊ ኮሚቴ ሰብሳቢ በሰጡት ምላሽ የአንቀጹ ርዕስ ወንጀሎችን ሳይሆን የወንጀል ሕግን እንደሚመለከት፣ በመሆኑም የወንጀል ሕግ ወደኋላ ተመልሶ እንደማይሠራ እንደሚገልጽ ፣ ለምሳሌ በአሁኑ ጊዜ እንደወንጀል ያልተወሰደ ተግባር ቢኖርና ወደፊት ግን እንደወንጀል ተወስዶ የሚያስቀጣ ከሆነ አንድ ሰው በአሁኑ ጊዜ ያንን ተግባር ፈጽሞ ቢቆይ በዚህ ድርጊት ምክንያት ወደፊት እንደማይቀጣ ፣ ስለዚህ አንቀጹ ርዕሱን ጨምሮ ማንኛውም ሰው ወንጀል ያልተባሉትን ሁሉ መሥራት ይችላል የሚል መንፈስ እንደማያመለክት ገልጸዋል ::

ከዚያም አቶ አሊ አብዱ ኢሴ ከክልል 5 ጉባኤው የሚወያይበት ሕገ መንግሥት በመፈቃቀድና በመተሳሰብ ላይ የተመሠረተች አዲስቷ ኢትዮጵያ የመገንባትን ሁኔታ መሠረት ያደረገ ሲሆን ቀደም ሲል ግን በማይታወቁና በጠፉ ወንጀለኞች አማካይነት በግለሰቦች ላይ በርካታ ወንጀሎች እንደተፈጸሙ ፣ በመሆኑም ለምሳሌ እ.አ.አ. በ1964 ዓ.ም በደጋሀቡር የተከሰተውን እንዲሁም የቅርብ ጊዜ ትውስታ በትግራይ ክልል በሀውዜን የተከሰተውን የሕዝብ መፍጀት ፣

በተመለከተ በሕግ የሚፈለጉ ሰዎች እንዳሉ ጠቅሰው አንቀጹ የሚፈለጉትን ወንጀለኞች ተከታትሉ እንዳይያዙ ያደርግ እንደሆነ ጠይቀዋል ::

የቀረበውን ጥያቄ በተመለከተ ወ/ሮ አረጋሽ አዳነ አንቀጹ በሕዝቦች ላይ ወንጀል የፈጸሙትን የደርግ ባለሥልጣኖች ጉዳይ እንደማይመለከት ፣ ሆኖም በአንቀጽ 28 በሕዝቦች ላይ ወንጀል የፈጸመ ሁሉ በይርጋ እንደማይታለፍ የተደነገገ በመሆኑ ለቀረበው ጥያቄ ምላሽ ሊሆን እንደሚችል ጠቁመዋል ::

በማስከተል አቶ ዳንኤል ደሴ ከክልል 4 በአንድ ወቅት ወንጀል ያልተባለ ድርጊት ተፈጽሞ ቢገኝ በኋላ እንደወንጀል ቢቆጠር ወደኋላ ተመልሶ ሊያስጠይቅ ይችላል ወይ ተብሎ የቀረበውን ጥያቄ በተመለከተ በማብራሪያው ገጽ 49 "ማንኛውም ሰው ድርጊቱን በፈጸመበት ጊዜ ድርጊቱ ወንጀል ሆኖ በሕግ ተደንግጎ ያልነበረ ከሆነ ከድርጊቱ በኋላ እንደወንጀል ሆኖ በሕግ አይቀጣም :: " ከሚለው ምላሽ ለማግኘት እንደሚቻል አስገንዝበዋል ::

ከዚያም አቶ መሀሙድ ድሪር ከክልል 5 አንቀጽ 223 የፍርድ ቤቶች ኮሚቴ ውይይት እንዳደረገበትና አንቀጹም የወንጀል ሕግ ወደኋላ ተመልሶ አይሠራም የሚለውን ሀሳብ እንደያዘ ፣ በውስጡ የማድረግና ያለማድረግ ሁኔታዎች እንደሚያካትት፣ በመሆኑም ሕጉ የሚፈጸሙትንና የሚከለከሉትን የደነገገ መሆኑን ከዚያ ውጭ ግን ማንኛው ሰው ወንጀለኛ ነው ተብሎ እንደማይቀጣ ፣ ለምሳሌ ድንጋጌው አንድን ሰው አትስረቅ ፣ አትግደል ብሎ እንደሚያስተምጥ ፣ በመሆኑም ያልሰረቀ ሆነ ያልገደለ ወንጀለኛ እንደማይሆን ፣ ከዚህ በተጨማሪም የሞራል ድርጊቶች እንዳሉ ለምሳሌ ልብስ ልበስ ወይም ልብስ መልበስ የሚል ሕግ አለመኖሩን ፣ ነገር ግን ማንኛውም ሰው ለኅብረተሰቡ ሞራል ብሎ ልብስ መልበስ እንዳለበት አመልክተዋል ::

በተጨማሪም የወንጀል ሕግ ወደኋላ ተመልሶ የማይሠራ ቢሆንም በንዑስ አንቀጽ 2 ላይ እንደተቀመጠው ድርጊቱ ከተፈጸመ በኋላ የወጣ ሕግ ለተከሳሹ ወይም ለተቀጣው ሰው ጠቃሚ ሆኖ ከተገኘ ከድርጊቱ በኋላ በወጣው ሕግ መሠረት ዳኛው ፍርዱን እንደሚሰጥ ጠቁመዋል ::

ከዚያም ወ/ሮ አረጋሽ አዳነ የሰብአዊና ዲሞክራሲያዊ መብት ኮሚቴ ሰብሳቢ ወንጀሎች እንዲሠሩ የሚያደርግ ሳይሆን በአንድ ወቅት ወንጀል ያልነበረ በሌላ ወቅት ወንጀል ከሆነ ሰውየው ድርጊቱን በፈጸመበት ጊዜ የነበረው ሕግ እንጂ በሌላ በሚወጣ ሕግ ተጠያቂ አይሆንም ለማለት እንደሆነ ፣ ንዑስ አንቀጽ 2 ደግሞ ማንም ሰው ወንጀለኛ ተብሎ ሲታሰር በነበረው ሕግ መዳኘት እንዳለበትና የተቀየረው ሕግ ለታሰረው ሰው የሚጠቅም ከሆነ ግን ከተቀየረው ሕግ አንፃር ሊታይለት



እንደሚችል እንደሚያመለክት ፣ ስለዚህ ይህ ድንጋጌ በተቻለ መጠን የሰብአዊ መብት ተገቢ በሆነ ጥልቀት ባለው መንገድ ተግባር ላይ እንዲውል ስለሚጠቅም ትክክለኛ እንደሆነ አብራርተዋል ::

ቀጥሎም አቶ ዓለምሰገድ ገ/አምላክ ከክልል 1 የወንጀለኛ መቅጫ ሕግ በሕግ ወንጀል ተብሎ የተቀመጡ ጥፋቶችን የሚዳኝ ሕግ እንጂ በፍትሐ ብሔር የሚያስ ጠይቁ ጉዳዮችን የሚመለከት እንዳልሆነ ፣ ስለዚህ በፍትሐ ብሔር ሊያስጠይቁ የሚችሉት ድርጊቶችን የፈጸመ ሰው በፍትሐ ብሔር ሕግ መሠረት እንጂ በወንጀለኛ መቅጫ እንደማይቀጣ ፣ ወንጀለኛ መቅጫ የሚባለው አብዛኛው በአንድ ወቅት የፀደቀ ቢሆንም ወንጀለኛ መቅጫው ከጊዜው ሁኔታ የሚጨምራቸው ሕጎች ስላሉ በየጊዜው እየዳበረ የሚሄድ መሆኑን ፣ በመሆኑም የወንጀለኛ መቅጫ ሕግ የሚባለው ቀደም ሲል የፀደቀውና ከዚያ በኋላም ወንጀልን በተመለከተ የወጡ ሕጎችን በማካተት መሆኑን ፣ ለምሳሌ አውሮፕላንን አስገድዶ መጥለፍ በወንጀለኛ መቅጫ ሕግ እንዳልነበረ ፣ በቅርብ ጊዜ ጉዳዩን የተወከሉት ምክር ቤት ተመልክቶ አዲስ ሕግ ማውጣቱን ፣ ስለዚህ ይህ ሕግ የወንጀለኛ መቅጫ ሕግ አካል እንደሆነ ፣ ከዚህም አንፃር ሲታይ መጀመሪያ ብዙ ጉዳዮችን በማካተት የወጣውና በኋላም እየዳበረ በሂደው የወንጀለኛ መቅጫ ሕግ ውስጥ እንደተፋፋት ያልተደነገገ ወንጀል ሊያስጠይቅ እንደማይችል ፣ ይህ የሚሆነው ግን በፍትሐ ብሔር ሕግ ፣ በንግድ ሕግ ወይም በሌሎች ሕጎች /ኮዶች/ የማያስቀጣ መሆኑን ፣ በመሆኑም አንቀጹ በሕግ ያልተካተተ ወንጀል ከተሠራ በኋላ ሕግ በማውጣት ወደኋላ መልሶ መጠቀም አለመቻሉንና ሕጉ የሚያገለግለው ሕጉ ከወጣ በኋላ ለሚፈጸም ወንጀል መሆኑ እንደሚያመለክት አስገንዝበዋል ::

አያይዘውም አንቀጹ በሰው ላይ ከፍተኛ ወንጀል የፈጸሙ ሰዎች ነፃ እንዲሆኑ እንደማያደርግ ፣ በመሆኑም ፋሽስታዊም ሆነ ዲሞክራሲያዊ መንግሥት በሰው ላይ የሚፈጸም ጥፋት ወንጀል መሆኑን በሕጋቸው እንደሚደነግጉ ለምሳሌም ደርግ በሰብአዊ ፍጡር ላይ የፈጸመው ጥፋት በሕግ እንደሚያስጠይቅ ቀደም ሲል በወንጀለኛ መቅጫ የተደነገገውን ሳይሰርዝ ጥፋት መፈጸሙን ፣ ስለዚህ በደርግ ጊዜ በነበረው ሕግ መሠረት በደርግ ጊዜ የተፈጸመ ግፍን መጠየቅ እንደሚቻል አመልክተዋል ::

አክለውም በአንቀጽ 28 ላይ በሰው ልጅ ላይ የሚፈጸም ወንጀል በይርጋ አይታገድም የሚለው በአሁኑ ወቅት በእስር ላይ ያሉ የደርግ ባለሥልጣኖች በምህረት እንዳይፈቱ መከላከያ መንገድ እንዳልሆነ ፣ ጉባኤው እየተወያየበት ያለው ሕገ መንግሥት ለወደፊቷ ኢትዮጵያ እንደሚያገለግልና በማንኛውም ጊዜ በሰብአዊ

ፍጡር ላይ ወንጀል የሚፈጽም ማንም ኃይል ምህረት አይሰጥም ብሎ እየዛ... መሆኑን ስለዚህ ጥፋተኛ ምህረት የማግኘት ዕድል ይኖረኛል ብሎ እንዳይጠብቅ... እንደሚያደርግ ፤ ስለጉዳዩም የጉባኤው ውይይት በአንቀጹ ላይ ሲደርስ በሰፊው ለማየት እንደሚችል አብራርተዋል ።

በመጨረሻም በጉዳዩ ላይ በቂ ውይይት ስለተካሄደበትና ለቀረቡትም ጥያቄዎች በቂ ምላሽ መሰጠቱን ቤቱ በመስማማቱ ውሳኔ ወደማስተላለፍ የተሸጋገረ ሲሆን አንቀጽ 22 በረቂቁ ባለው መልኩ እንዲፀድቅ ለድምፅ ቀርቦ በሙሉ ድምፅ ተደገፈ... ከፀደቀ በኋላ የዕለቱ ውይይት 12 05 ሰዓት ተጠናቋል ።



ኅዳር 6 ቀን 1987 ዓ.ም ከጧቱ በ3:00 ሰዓት በሕገ መንግሥት ጉባኤ አዳራሽ የተጀመረው የኢትዮጵያ ሕገ መንግሥት ጉባኤ ስብሰባ የተመራው በጉባኤው ሊቀመንበር በዶ/ር ነጋሶ ጊዳዳ ሲሆን በመጀመሪያ የጉባኤው ዋና ፀሐፊ አቶ አዲሱ ለገሠ በዕለቱ 520 የጉባኤ አባላት የተገኙ በመሆኑ ስብሰባውን መጀመር እንደሚቻል ከአስታወቁ በኋላ የጉባኤው ሊቀመንበር የዕለቱ አጀንዳ ፤

1. የኢትዮጵያ ሕገ መንግሥት ጉባኤ ቃለጉባኤ ቁጥር 7 እና 8 ማፅደቅ ፤
2. በረቂቅ ሕገ መንግሥቱ ላይ የተጀመረውን ውይይት መቀጠል ፤

የሚል መሆኑን ገልጸዋል ።

በመጀመሪያ የጉባኤው ሊቀመንበር በኢትዮጵያ ሕገ መንግሥት ጉባኤ ቃለጉባኤ ቁጥር 7 ላይ የማሻሻያ ሆነ የቀረ ሀሳብ ካለ ማቅረብ እንደሚቻል ባሳሰቡት መሠረት ፤

- ገጽ 9 አምስተኛው ፓራግራፍ "አቶ ካሪቴ ጉሉ" የሚለው አቶ ካሪቴ ገሉ ፤
- ገጽ 10 በአራተኛው ፓራግራፍ "... በድምፅ ብልጫ ሳይሆን በኮንሰንሰስ ." የሚለው ... "በድምፅ ብልጫ ሳይሆን በከልሉች ኮንሰንሰስ ." ፤
- ገጽ 15 አንደኛው ፓራግራፍ "አቶ ማርቆስ ሌለንጎም" የሚለው "አቶ ማርቆስ ሊራንጎም " ፤
- ገጽ 15 የመጨረሻው ፓራግራፍ "አቶ ሙሉጌታ ገ/እምላክ" የሚለው " አቶ ሙሉጌታ ገ/ሕይወት " ፤
- ገጽ 20 ሁለተኛው ፓራግራፍ አራተኛው መስመር "አቶ ወንድሙ ቱር ብሔረሰባቸው ሳሌ" የሚለው "ብሔረሰባቸው ኩሬ" ፤
- ገጽ 20 ሁለተኛው ፓራግራፍ አስራ አንደኛው መስመር ላይ "ኢብራሂም አህመዲን" የሚለው "አብዱራሂም መሐመድ" ፤
- ገጽ 22 መጀመሪያው ፓራግራፍ መጨረሻው መስመር "መቀፈፉን" የሚለው " መፈቀዱን" ፤

ተብሎ እንዲስተካከል ተጠይቆ ተቀባይነትን አግኝቷል ።

የኢትዮጵያ ሕገ መንግሥት ጉባኤ ቃለጉባኤ ቁጥር 8

- ገጽ 2 ሦስተኛው መስመር ላይ "አቶ ኒሃልጋች ዲንግ" የሚለው "አቶ ኒሃልጋች ደንግ" ፤
- ገጽ 2 አራተኛው መስመር ላይ "አቶ ቀኝያለው ሣለ" የሚለው "አቶ ቀኝያለው ሀሌ" ከአራሺ ብሔረሰብ የሚለው ከደራሺ ብሔረሰብ" ፤

- ገጽ 3 መጀመሪያው መስመር ላይ "አቶ አበበ አበራ" የሚለው "አቶ ደበበ አበራ" ፣
- ገጽ 4 ተራ ቁጥር 5 "አቶ መሐመድ ሼክ መሐመድ" የሚለው "አቶ መሐመድ ሼክ ሙሐመድ " ፣
- ገጽ 4 ተራ ቁጥር 9 "አቶ ኢብራሂም ዘካሪያስ" የሚለው "አቶ ኢብራሂም ዘካሪያ" ፣
- ገጽ 4 መጨረሻው ፓራግራፍ መጨረሻውጭ መስመር "... እያባሰሉ" የሚለው "እያበሰሉ" ፣
- ገጽ 6 መጨረሻው ፓራግራፍ መጀመሪያው መስመር "አቶ መሐመድ ድሪር" የሚለው "አቶ መሀሙድ ድሪር" ፣
- ገጽ 9 ሁለተኛ ፓራግራፍ የመጀመሪያ መስመር ላይ "... ሕገ መንግሥቱ ላይ እንወያይበት" የሚለው "ሕገ መንግሥቱ ላይ እንወያይበት" ፣
- ገጽ 17 አንደኛው ፓራግራፍ ሁለተኛው መስመር ዐረፍተ ነገር "... ስርዓት ... አስረድተዋል ::" የሚለው "... ለምሳሌ በሲዊዘርላንድ ጀርመኖች ጣሊያኖች ሁኔታዎች ስለተመቻቹላቸው ባህላቸውንና ቋንቋቸውን በማሳደግ ከሌሎች ነዋሪዎች ጋር ተባብረው እንደሚኖሩ አመልክተዋል ::" ፣
- ገጽ 19 ሁለተኛው ፓራግራፍ መጀመሪያ መስመር ላይ "... ክክልል በበኩላቸው ... "የሚለው "... ከክልል 1 በበኩላቸው" ፣
- ገጽ 19 መጨረሻው ፓራግራፍ መጀመሪያ መስመር ላይ "... ይህሕዝቡን..." የሚለው "... የሕዝቡን ..." ፣

ተብሎ እንዲስተካከል ተጠይቆ ተቀባይነት አግኝተዋል ::

የኢትዮጵያ ሕገ መንግሥት ጉባኤ ቃለጉባኤ ቁጥር 7 እና 8 ከነማሻሻያዎቻቸው በየተራ ድምፅ ተስጥቶባቸው በሙሉ ድምፅ ፀድቀዋል ::

ቀጥሎም ጉባኤው በረቂቅ ሕገ መንግሥቱ ላይ ጀምሮት የነበረውን ውይይት ከቆመበት አንቀጽ 23 በመጀመር የቀጠለ ሲሆን አንቀጹን ምክትል ፀሐፊው በንባብ ካሰሙ በኋላ የጉባኤው ሊቀመንበር የሰብአዊና ዲሞክራሲያዊ መብት ኮሚቴ ርዕሱ "በአንድ ወንጀል ድጋሚ ክስና ቅጣት ስለመከልከሉ" በሚል ተሻሽሎ አንቀጹ ቤቱ እንዲያፀድቀው መጠየቁን አውስተው በጉዳዩ ላይ አስተያየት ካለ ማቅረብ እንደሚቻል ገልጸዋል ::

በዚሁም መሠረት አቶ ሙሉጌታ አመና ከክልል 4 አንድ ሰው በወንጀል ተከሶ ፍርድ ቤት ከቀረበ በኋላ በቂ ማስረጃ ሳይገኝ ቀርቶ ፍርድ ቤቱ በነፃ



ከለቀቀው በኋላ ... ከክስ ...

ከስናበተውና ከጊዜ በኋላ በቂ ማስረጃ ከተገኘ ድጋሚ አይከሰስም ማለት ነው ወይ ? የሚል ጥያቄ ያቀረቡ ሲሆን በተጨማሪም አንድ ሰው በወንጀል ከተከሰሰ በኋላ ድጋሚ በፍትሐ ብሔር ተከሶ እንዳይጠየቅ ያደርጋል ወይ ? በተመሳሳይ ወንጀል ድጋሚ መሳተፍ እንዴት ይታያል ? የሚሉ ጥያቄዎችም ከሌሎች የጉባኤው አባላትም ተነስተዋል ::

የሰብአዊና ዲሞክራሲያዊ መብት ኮሚቴ ሰብሳቢ ወ/ሮ አረጋሽ አዳነ ለቀረቡት ጥያቄዎች በሰጡት መልስ አንድ ሰው ከዚህ ቀደም ተከሶ በተቀጣበት ወይም በነፃ በተለቀቀበት አንድ ጉዳይ ላይ በድጋሚ አይከሰስም የሚል መንፈስ እንዳለው ገልጸው ማስረጃ ማሰባሰብም ሆነ ብቃቱን መመዘን የሚመለከተው አካል ያከናወነው ቅድመ ውሳኔ ተግባር እንደሚሆንና ያለ ማስረጃም ውሳኔ እንደማይሰጥ የማስረጃ እጥረት ካጋጠመም ነገሩን በእንጥልጥል ማቆየት እንደሚቻል አስረድተዋል ::

አስከትሉም የጉባኤው ሊቀመንበር አንድ ሰው ተከሶ በተገኘው ማስረጃ ከተፈረደበት በኋላ ውሳኔውን የሚያስቀይር ማስረጃ ቢቀርብ እንዴት ? ይሆናል የሚል ጥያቄ አቅርበው ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ አንድ ሰው ሰው ገድልሀል ተብሎ ከተፈረደበት በኋላ አፍራሽ ማስረጃ ከተገኘ እንደሚለቀቅ ገልጸዋል ::

በሌላ በኩል ደግሞ አቶ አበበ ጎበና ከክልል 6 የርዕሱን ማሻሻያ በመቃወም በሰጡት አስተያየት የአንድ ክስ ፍሬና ገለባው የሚታወቀው ፍርድ ቤት ቀርቦ ከታየ በኋላ በመሆኑ በደፈናው ክስ አይቀርብም ማለት ትክክል እንዳልሆነና ርዕስ ሳይሻሻል አንቀጹ በረቂቁ ላይ በተቀመጠው መልክ ቢሆን የተሻለ እንደሆነ አመልክተዋል ::

ይህንን በተመለከተ የሰብአዊና ዲሞክራሲያዊ መብት ኮሚቴ ሰብሳቢ ወ/ሮ አረጋሽ አዳነ በሰጡት አስተያየት በርዕሱ የተደረገው ማሻሻያ አንቀጹ ያስተላልፈው ከነበረው መልዕክት የተለየ እንዳልሆነ ጠቁመው አንድ ሰው ከዚህ በፊት በተከሰሰበት ወንጀል እንደገና ተከሶ ፍርድ ቤት ይቀርባል የሚለው ሀሳብ የሚፃረረው የኮሚቴው ማሻሻያ ሳይሆን አንቀጹ በመሆኑ ትክክል እንዳልሆነና የኮሚቴው ማሻሻያ ተገቢ መሆኑን አመልክተዋል ::

ከዚያም አቶ ሙሉጌታ ገ/ሕይወት ከክልል 1 በበኩላቸው በረቂቁ ባለው መልክ አቃቤ ሕግ ክስ መሥርቶ ማስረጃ ቢያጣና ክሱን እያንጠለጠለ መቀጠል ካልቻለ ክሱን አንስቶ በቂ ማስረጃ ሲያገኝ እንደገና ክስ ከመመስረት የሚያግደው ሲሆን

ርዕሱ ኮሚቴው ባቀረበው መልኩ ከተሻሻለ ግን ይህን ሊዘጋ ስለሚችል ቤቱ ያለማሻሻያ አንቀጹን ቢቀበለው የተሻለ እንደሚሆን ገልጸዋል ::

ቀጥሎም የጉባኤው ዋና ፀሐፊ አቶ አዲሱ ለገሠ በበኩላቸው አንቀጹ በአንክሮ ከታየ የርዕስ ለውጥ እንደማያስፈልገው በሰጡት አስተያየት ርዕሱ በኮሚቴው ማሻሻያ ሀሳብ መሠረት ከተቀየረ አንድ ወንጀለኛ በቂ ማስረጃ ባልተገኘበት ጊዜ ተለቆ ማስረጃ ቢገኝ እንደገና አይከሰስም የሚል እንድምታ ስለሚሰጥ በአንቀጹ ከተጠቀሰው የወንጀለኛ መቅጫ ሥነ ሥርዓት ጋር ስለሚፃረር አንቀጹ በረቂቁ ባለው መልኩ ቢቀመጥ እንደሚሻል ጠቁመዋል ::

አስከትሎም አቶ ዚያድ ዳውድ ከክልል 5 ማስረጃ ሳይጠናቀር አንድ ግለሰብ ለፍርድ እንደማይቀርብ ነገር ግን በተለያዩ ሁኔታዎች አንድ ሰው ባልሠራው ወንጀል ጥፋተኛ ነህ ተብሎ ሊቀጣ እንደሚችልና በአንፃሩም ደግሞ ወንጀለኛው በማስረጃ እጦት ነፃ የሚሆንበት ሁኔታ ሊኖር እንደሚችል ገልጸው አንቀጹ በወንጀለኛ መቅጫ ያለና ዓለም አቀፋዊ ባህሪይ ያለው እንዲሁም መንፈሱ ከሕግ አኳያ ሲታይ ትክክል በመሆኑ ብዙ ክርክር ባይደረግበት ይሻላል ሲሉ አስገንዝበዋል::

በሌላ በበኩል አቶ አህመዲን ኢብራሂም ከክልል 4 አንቀጽ 23ን አስመልክተው በሰጡት ማብራሪያ ሀሳቡ የይግባኝ መብት እንደተጠበቀ ሆኖ አንድ ክስ በአንድ ፍርድ ቤት እየታየ ወይም ከታየ በኋላ በውሳኔው አልረካሁም በሚል በዚያው ጭብጥና ማስረጃ በሌላ ፍርድ ቤት ክስ እንዳይመሠርት ለመከላከል መሆኑን ገልጸው ተጨማሪ ማስረጃ ከተገኘ ግን በዚያው ፍርድ ቤት ክሱ እንዲታይ ማድረግ እንደሚቻል አብራርተዋል ::

ወ/ሮ አረጋሽ አዳነ የሰብአዊና ዲሞክራሲያዊ መብት ኮሚቴ ሰብሳቢ ርዕሱ ኮሚቴው ባሻሻለው መልኩ መቀመጡን በመቃወም የቀረቡት ምክንያቶች አሳማኝ እንዳልሆኑ ጠቅሰው ርዕሱ በረቂቁ ላይ እንደነበረ ቢቀመጥ ተፈላጊውን መልዕክት አያስተላልፍም የሚል ግምት ስለሌላቸው እንዳለ ቢሆን እንደማይቃወሙ ገልጸዋል ::

ከዚያም አንቀጽ 23 በረቂቁ ላይ ባለው መልኩ እንዲቀመጥ ለድምፅ ቀርቦ ድጋፍ 520 ፣ ተቃውሞ 2 ፣ ድምፀ ተአቅቦ 2 በመመዝገቡ አንቀጽ 23 በረቂቁ ባለው መልኩ ያለምንም ማሻሻያ ፀድቋል ::

ቀጥሎም ጉባኤው ውይይቱን በአንቀጽ 24 ላይ የቀጠለ ሲሆን የጉባኤው ምክትል ፀሐፊ አቶ አባተ ኪሾ አንቀጹን በንባብ ካሰሙ በኋላ የጉባኤው ሊቀመንበር የሰብአዊና ዲሞክራሲያዊ መብት ኮሚቴ በአንቀጽ 24 ንዑስ አንቀጽ 2 ላይ "ዜጎች" የሚለው ቃል "ሰዎች" በሚል እንዲተካ የማሻሻያ ሀሳብ ማቅረቡን አስታውቀው ቤቱ በማሻሻያ ሀሳቡ ላይ አስተያየት ካለው ሊቀርብ እንደሚችል ገልጸዋል ::



በዚሁ መሠረት አቶ ዓለምሰገድ ገ/አምላክ ከክልል 1 ማሻሻያውን በተመለከተ በሰጡት አስተያየት የተወካዮች ምክር ቤት "ዜጎች" የሚለውን ቃል ለምን እንደመረጠ ኮሚቴው ተገንዝቦ ከሆነ ማብራሪያ እንደሰጥበት ጠይቀው በበኩላቸው ግን "ዜጎች" የሚለው ቃል የተመረጠው ዜጋ ያልሆነ ሰው ዜጋ በሆነ ሰው ማንነት ላይ ጫና እንዳያሳድር ሆን ተብሎ የተቀመጠ ይሆናል የሚል ግምት እንዳላቸው ጠቅሰዋል ::

የሰብአዊና ዲሞክራሲያዊ መብት ኮሚቴ ሰብሳቢ ወ/ሮ አረጋሽ አዳነ ለቀረበው ጥያቄ በሰጡት ማብራሪያ የቃል ለውጡ ሀሳብ ከአማካሪዎች የተገኘ መሆኑን ጠቁመው በንዑስ አንቀጹ መጀመሪያ ላይ "ማንኛው ሰው" ሲል ዜጎችንም ሆነ ዜጎች ያልሆኑትን ስለሚያጠቃልል እና ከሰብአዊ መብቶች አንፃር የተቀመጠ በመሆኑ አንድ ሰው ስብዕናውን ከሌሎች ዜጎች መብቶች ጋር ብቻ ሳይሆን ዜጎች ካልሆኑ ሰዎች መብቶች ጋርም በማጣጣም በነፃ የማሳደግ መብት እንዳለው ማመልከት አለበት በሚል መነሻ "ዜጎች" የሚለው ቃል "ሰዎች" በሚል መተካት ማስፈለጉን ገልጸው ሰብአዊ መብቶች ለዜጎች ብቻ ሳይሆን ለሌሎችም የሚሰጥ በመሆኑ ቃሉ ይበልጥ ገላጭ መሆኑን ፣ የተወካዮች ምክር ቤት ዜጎች የሚለው ቃል ከምን አኳያ እንዳስቀመጠው ያላጤኑት መሆኑን አብራርተዋል ::

ቀጥሎም አቶ አህመድ ሀሰን ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል በሰጡት አስተያየት በየትኛው አገር ዜጎች የተለያዩ መብቶች እንዳሏቸው ፣ የአንድ የውጭ አገር ዜጋ መብት ከአገሬው ተወላጅ እኩል ሳይሆን አገሪቱ ዜግነትን በተመለከተ በምትከተለው ሕግ እንደሚወሰን አመልክተው በንዑስ አንቀጹ "ዜጎች" የሚለው ቃል "ሰዎች" በሚል ከተተካም ማንኛው የውጭ ዜጋ ኢትዮጵያ ውስጥ ከመጣ እንደኢትዮጵያውያን መብት አለው የሚል የተሳሳተ እንድምታ እንዳይሰጥ እንደሚሠጉና የምክር ቤቱ አስተሳሰብም ይኸው እንደሚመስላቸው ገልጸዋል ::

የጉባኤው ፀሐፊ በበኩላቸው የተወካዮች ምክር ቤት ባቀረበው ማብራሪያ በገጽ 53 ፣ 5ኛው ፓራግራፍ ላይ "ማንኛውም ሰው የሌሎቹን ዜጎች መብቶች በማይፃረር መንገድ ስብዕናውን ማሳደግ ይችላል ::" የሚል በመሆኑ በረቂቁ ላይ በተጣጣመ ሁኔታ የሚለው ከዚያ በመነሳት መሆኑን ፣ ስለዚህ እንደነበረ መቀመጡ ጉዳት ስለሌለው እንዳለ ቢቀመጥ እንደሚሻል ገልጸው ዜጎች የሚለው ሰዎች በሚለው ከተተካ ግን ሌሎች ዜጎች እንደመብት የተሰጣቸውን የሚጋፋ ወይም የሚቀንስ

እንደሚሆን አመልክተዋል ። አቶ ዓለምሰገድ ገ/አምላክ ከክልል 1 አንቀጹ በረቂቁ በተቀመጠው መልኩ እንዳለ ቢፀድቅ የሚደግፉ መሆናቸውን አስታውቀዋል ።

በሌላ በኩል አቶ ዚያድ ዳውድ ከክልል 5 አንቀጹ ሰዎች ሰብአዊ ፍጡር በመሆናቸው ሰብአዊ መብታቸው እንደሚከበር የሚያረጋግጥ ቢሆንም ጉባኤው የሚመለከተው የኢትዮጵያውያንን ሰብአዊ መብት ስለሆነ አንቀጹ ኢትዮጵያውያንን ብቻ በሚያመለክት መልኩ መቀመጥ እንዳለበት ጠቁመው በተቀመጠው መልኩ ግን በአገር ውስጥ ያሉ የውጭ ዜጎችንም ሊመለከት እንደሚችልና እነዚህም የውጭ ዜጎች ከኢትዮጵያውያን እኩል መብት የሚኖራቸው የኢትዮጵያ ዜግነት መብት ሲያገኙ ብቻ እንደሆነ ገልጸዋል ።

ከዚያም የጉባኤው ምክትል ጸሐፊ አቶ አባተ ኪሾ በበኩላቸው ሰው ሰው በመሆኑ ብቻ ሰብአዊ ክብሩ መከበር እንደለበት የሁሉም እምነት እንደሆነ ፣ ሰብአዊ ክብርን ለመጠበቅ የቀለም ፣ የፆታ ፣ ወዘተ... ልዩነቶች የማይደረጉ በመሆናቸው የአገርና የውጭ ዜጋ በሚል የሚቀመጥ አለመሆኑን ፣ ክብርንና መልካም ስምን የመጠበቅ መብትም ለሰው ልጅ የተሰጠ መሆኑን መቀበል እንደሚያስፈልግ አስረድተው አንቀጹ እንዳለ ቢቀመጥ እንደሚሻል አሳስበዋል ።

በመጨረሻም የጉባኤው ሊቀመንበር በአንቀጹ ላይ ቤቱ በቂ ውይይት ስለደረገበት ወደውሳኔ ሀሳብ እንዲሸጋገር ያቀረቡትን ሀሳብ ቤቱ ስለደገፈው አንቀጽ 24 በረቂቁ ላይ በተቀመጠው መልኩ እንዲፀድቅ ለድምፅ ቀርቦ ከአንድ ድምፀ ተአቅቦ በስተቀር በተቀሩት የጉባኤው አባላት ተደገፎ ፀድቆ ጉባኤው ለሻይ ዕረፍት 5:45 ተነስቷል ።

ጉባኤው ከሻይ ዕረፍት በኋላ የእኩልነት መብት በሚለው በአንቀጽ 25 ወይይቱን የቀጠለ ሲሆን በቅድሚያ አንቀጹ በጉባኤው ምክትል ጸሐፊ በአቶ አባተ ኪሾ በንባብ ከተሰማ በኋላ የጉባኤው ሊቀመንበር የሰብአዊና ዲሞክራሲያዊ መብት ኮሚቴ አንቀጹ እንዳለ እንዲፀድቅ ሀሳብ ማቅረቡን አስታውቀው ከዚህ የተለየ ሀሳብ ካለ ማቅረብ እንደሚቻል ገልጸዋል ።

በዚህም መሠረት ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ ከክልል 14 የሴቶችንና የወንዶችን እኩልነት ከሚሽሩት ጉዳዮች አንዱ የውርስ መብት መሆኑንና ይህም ወንዱ ከሞተ ሴቷ ውርስታውን ልትወርስ እንምትችል ፣ ሴቷ ከሞተች ግን ወንዱ ውርስታዋን ሊወርስ እንደማይችል ጠቅሰው ጉዳዩ በሕገ መንግሥቱ እልባት ማግኘት አለበት ሲሉ አሳስበዋል ። ሆኖም ጉዳዩ በሴቶች መብት የሚታይ መሆኑንና ጠቋመው ጉዳዩ በአንቀጽ 35 ንዑስ አንቀጽ 7 ላይ መልስ ማግኘቱን የጉባኤው ሊቀመንበር አመልክተዋል ።



በሌላ በኩል ደግሞ የእኩልነት መብት በሕገ መንግሥቱ ቢደነገግም አስፈጻሚ አካላት በተለያዩ ምክንያቶች በሰዎች መካከል ልዩነቶች ሊፈጥሩ ፣ ፍትሕን ሊያዛቡና የአስተዳደር በደል ሊያደርሱ ስለሚችሉ በአጠቃላይ የዜግነትና የእኩልነት መብቶች እንዲጠበቁ በጥብቅ እየተከታተለ እገዛ የሚያደርግ አካል እስከ ቀበሌ ድረስ ባሉት የአስተዳደር እርከኖች እንዲቋቋም በአንቀጹ ይገለጽ የሚል ሀሳብ በአቶ ኃይለማርያም ተክሉ ፣ በአቶ ሰኢድ ሬድዋንና በአቶ መሐመድ ሼክ አህመድ ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል ሀሳብ ቀርቦ በአንቀጽ 55 ንዑስ አንቀጽ 15 ላይ የሕዝብ እምባ ጠባቂ ተቋም እንደሚቋቋም የሚደነግግ መሆኑ ተገልጾ ጉዳዩ ታልፏል ።

ከዚያም በአንቀጹ ላይ ተጨማሪ የማሻሻያ ሀሳብ ባለመቅረቡ ኮሚቴው ባቀረበው መልኩ አንቀጹ በረቂቁ ላይ በተቀመጠው መልኩ እንዲፀድቅ ለድምፅ ቀርቦ በሙሉ ድምፅ ፀድቋል ።

ቀጥሎም ጉባኤው መወያየት የጀመረው በአንቀጽ 26 ሲሆን በቅድሚያ የጉባኤው ምክትል ፀሐፊ አንቀጹን በንባብ ለቤቱ ካሰሙ በኋላ የጉባኤው ሊቀመንበር የሰብአዊና ዲሞክራሲያዊ መብት ኮሚቴ አንቀጹ በረቂቁ በተቀመጠው መልኩ እንዳለ እንዲፀድቅ ሀሳብ ማቅረቡን አስታውቀው ከዚህ የተለዩ ሀሳብ ካለ ማቅረብ እንደሚቻል ገልጸዋል ።

በዚህም መሠረት ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ ከክልል 14 በማናቸውም ዘዴ የሰውን ውይይትና ሚስጥር መቅረጽ የተወገዘ እንደሆነ ፣ የአሜሪካ ፕሬዚዳን ኒክሰን የፖለቲካ ተቃዋሚዎችን ሚስጥር በመቅዳታቸው ከሥልጣን እንደወረዱ ፣ በአፄ ኃይለ ሥላሴ ዘመነ መንግሥትም 300 ያህል ቴፕ ሪከርደሮች በተጠርጣሪ ግለሰቦች ላይ ይጠቀምበት እንደነበር አስታውው በቻርተሩ ተከልክሎ እያለ ኢሕአዴግ በግዮን ሆቴል የተካሄደውን የሰላምና የእርቅ ኮንፈረንስ ሂደት በድብቅ በመቅዳት በሬድዮ ጣቢያው አሰራጭቶ እንኳን ከሥልጣን ይውረድ ጥያቄም ሆነ ወቀሳ ስላልቀረበበት በጉዳዩ ላይ ጉባኤው ተወያይቶ አንድ እርምጃ እንዲወስድ ጠይቀው ይህ ካልሆነ ግን ለይስሙላ እንደሚጻፍ ገልጸዋል ።

ለዚህም የጉባኤው ሊቀመንበር በሰጡት ምላሽ የጉባኤው ተግባር ከዚህ በፊት በአገሪቱ በተከናወኑ ጉዳዮች ላይ በሚቀርቡ ክሶች ፍርድ ለመስጠት ሳይሆን ረቂቁ ሕገ መንግሥቱን መርምሮ ማፅደቅ እንደሆነ አስታውቀዋል ።

አስከትሎም አቶ መሐመድ አህመድ ከክልል 3 በአንቀጽ 26 ላይ የተጠቀሱ የግል ሕይወት የመከበርና የመጠበቅ መብቶች በንዑስ አንቀጽ 3 መሠረት አስገዳጅ ሁኔታዎች ሲፈጠሩ ሊገደቡ እንደሚችሉ መቀመጡን አውስተው አስገዳጅ

ሁኔታዎች መፈጠራቸውን የሚያረጋግጠው አካል ማን እንደሆነና ይህ አካል ሁኔታዎች መፈጠራቸውን የሚያረጋግጠው አካል ማን እንደሆነና ይህ አካል አስገዳጅ ሁኔታዎች ሳይፈጠሩ ተፈጥረዋል ቢል ችግሩን ማን እንደሚፈታው ማብራሪያ እንደሰጥበት ጠይቀዋል ።

በሌላ በኩል አቶ ለማ ፊጣ ከክልል 4 አንድ ሰው ንብረቱን ያሸሻል በሚል ያለፍርድ ቤት ትዕዛዝ ወይም ውሳኔ ንብረቱ ሊያዝ ስለሚችል ንብረቱ ያለ ሕግ ሊያዝ እንደማይችል በሚገልጽ መልኩ አንቀጽ 26 ንዑስ አንቀጽ 1 እንዲሻሻል ሀሳብ አቅርበዋል ።

ከዚያም አቶ መሀመድ ድሬር ከክልል 5 በበኩላቸው በአንቀጽ 26 ንዑስ አንቀጽ 3 መሠረት አስገዳጅ ሁኔታዎች መፈጠራቸው የሚያረጋግጠው ማን እንደሆነ በረቂቅ ሕገ መንግሥቱ አንቀጽ 95 ላይ መጠቀሱን አስታውሰው በንዑስ አንቀጹ ከጤና አኳያ የግል ሕይወት የመከበርና የመጠበቅ መብቶች እንዴት ሊገደቡ እንደሚችሉ ሊብራራላቸው ጠይቀው አቶ ተሰፋዬ ሻረው ከክልል 14 በሰጡት ምላሽ ኅብረተሰቡን ሊጎዳ የሚችል ወረርሽኝ ከተፈጠረ ወረርሽኙ እንዳይስፋፋ የግል ሕይወት መብት ሊገደብ እንደሚችል ፣ ይህም የሚሆነው የብዙሃኑን መብት ለማስከበር እንደሆነ ገልጸዋል ።

በሌላ በኩል አቶ አዳሙ ደገፉ ከክልል 14 ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ ከክልል 14 ኢሕአዴግ በግዮን ሆቴል የሰላምና የእርቅ ኮንፈራንስ ሂደት በቴፕ በመቅዳት በሬድዮ ጣቢያው በማሰራጨቱ ጉባኤው ተወያይቶ ውሳኔ ላይ እንዲደርስ ያቀረቡትን ሀሳብ በመደገፍ ሕገ መንግሥቱ ከፀደቀበት ጊዜ ጀምሮ ወደፊት የዚህ ዓይነት ስህተቶች እንዳይደገሙ ቤቱ አንድ ውሳኔ ሊያሳልፍ እንደሚገባው ሀሳብ አቅርበው ኢሕአዴግ ሚስጥር በመቅዳት በድሎኛል የሚል አካል ካለ በነፃ ፍርድ ቤት ሊከስ እንደሚችል የጉባኤው ሊቀመንበር አመልክተዋል ።

አቶ ዳንኤል በላይነህ ከክልል 14 መንግሥት የአንድን ግለሰብ ሚስጥር ለማወቅ ሲፈልግ የግለሰቡን ቤት እንደሚፈትሽ ፣ ለምሳሌም ፕሮፌሰር አስራት ወልደየስ ወደ እስር ቤት ከወረዱ በኋላ ቤታቸውንና ጽሕፈት ቤታቸውን እንደፈተሸ ጠቅሰው ለወደፊቱ የዚህ ዓይነቱ ሁኔታ እንዳይደገም ማንም ሰው ቤቱ ያለ ሕግ ሊፈተሽ እንደማይችል በሚያሳይ መልኩ አንቀጽ 26 ንዑስ አንቀጽ 1 እንዲሻሻል ሃሳብ አቅርበዋል ።

ከዚህ ሀሳብ በመነሳትም አቶ ዓለምሰገድ ገ/አምላክ ከክልል 1 አቶ ዳንኤል በላይነህ በመብት ደረጃ ለፕሮፌሰር አስራት ወልደየስ ጥብቅና ሊቆሙ ቢችሉም የተሳሳተ መረጃ ሊያቀርቡ እንደማይችሉ ፣ የፕሮፌሰር አስራት ወልደየስ ቤትና የመኢሕድ ጽሕፈት ቤት የተፈተሸው በፍርድ ቤት ትዕዛዝ መሠረት እንደሆነ አስገንዝበዋል ።



አያይዘውም ኢሕአዴግ የሰላምና የዕርቅ ኮንፈራንስ ሂደት በድብቅ በመቅዳት በሬድዮ አሰራጭቷል ተብሎ ከቀረበው ሀሳብ በመነሳት የኢሕአዴግ ሬድዮ ጣቢያ እንግንኛው ዜና ማሰራጫዎች መረጃ የማግኘትና የማሰራጨት መብቱን በመጠቀም ኮንፈራንሱን በተመለከተ ያገኘው መረጃ የአገርን ደህንነት አደጋ ላይ የሚጥል መሆኑን አረጋግጦ ማስተላለፉን ከፕሬዚዳንት ኒክሰን ከሥልጣን መውረድ ታሪክ ጋር ሊገናኝ እንደማይችል አብራርተዋል ።

በሌላ በኩልም ሻለቃ አድማሴ ዘለቀ ከክልል 14 የግልም ይሁን የጋራ ሚስጥር በድብቅ መቅረጹ ለወደፊቱ እንዳይፈጸም ምን ይሁን እንጂ ክስ ለጉባኤው እንዳላቀረቡ ገልጸዋል ።

ከዚያም ዶ/ር ተከተል ፎርሲዶ ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል የሕገ መንግሥት ጉባኤ የሀገሪቱን ረቂቅ ሕገ መንግሥት እያፀደቀ መሆኑን ገልጸው የዓለም ታሪኮች ሲገልጹ በትክክል ሊጠቅሱ እንደሚገባ አስገንዝበው ፕሬዚዳንት ኒክሰን ከሥልጣን የወረዱት በሻለቃ አድማሴ ዘለቀ እንደቀረበው የፖለቲካ ተቃዋሚዎችን ሚስጥር በድብቅ በመቅዳት ሳይሆን የተቃዋሚዎችን ጽሕፈት ቤት ስላሰበሩና ስላዘረፉ እንደሆነ ፣ የአንድ ሰው የግል ሕይወት የመከበርና የመጠበቅ መብቶች በሕግ መሠረት ሊገደቡ መቻላቸው "... በዝርዝር ሕጎች መሠረት ካልሆነ በቀር ..." በሚል በአንቀጽ 26 ንዑስ አንቀጽ 3 ላይ መቀመጡን ፣ መብቶች ለምሳሌ በአንድ አካባቢ ወረርሽኝ ከተከሰተ ወይም በጤና ላይ ጉዳት ሊያደርስ የሚችል ፈንጂ በአንድ ሰው ቤት መኖሩ ከተጠረጠረ ወዘተ... ሊገደቡ እንደሚችሉ ያስረዱ ሲሆን ቤቱ አንቀጹን ባለው መልኩ እንዲያፀድቀው ሀሳብ አቅርበዋል ።

ቀጥሎም ዶ/ር አብዱልመጂድ ሁሴን ከክልል 5 ለኅብረተሰቡ ጎጂ የሆኑ የአደንዛዥ ዕጾች አጠቃቀም በኢትዮጵያ እየተስፋፋ መሆኑን ጠቁመው የኅብረተሰቡን ጤና የሚጎዳ ከሆነ የአንድ ሰው ቤት ወይም ንብረት ሊፈተሽ እንደሚችል ፣ በዚህም የግል ሕይወት የመከበርና የመጠበቅ መብቶች ሊገደቡ እንደሚችሉ ለዚህ ሲባል "ጤና" የሚለው ቃል መብቶች ሊገደቡ የሚችሉበት ሁኔታ በሚገልጸው አንቀጽ 26 ንዑስ አንቀጽ 3 እንደገባ አስረድተዋል ።

በማስከተልም ሐጂ አብዱራህማን አብዱልቃድር ከክልል 13 ባለፉት ሥርዓቶች ብዙ ግፎች በኢትዮጵያ ሕዝቦች ሲፈጸሙ እንደነበር ፣ እነዚህ ግፎች እንዳይደገሙ ወደፊት ባለሥልጣኖች ፣ ዳኞች እንዲሁም ሌሎች ሥራአስፈጻሚ አካላት ለሕገ መንግሥቱ ተገዢ ሆነው እንዲሠሩ ጉባኤው ሕገ መንግሥቱን የሚያፀድቅ በመሆኑ

ስለአለፉት ሥርዓቶች ግፎች ብዙ ሊወሳ እንደማይገባው ገልጸው የአንቀጹ ንዑስ አንቀጾች እንደሉ ቤቱ እንዲያጸድቃቸው ሀሳብ አቅርበዋል ።

ከቤቱ አንቀጽ 26 ያለምንም መሻሻያ በረቂቁ ባለው መልኩ እንዳለ እንዲፀድቅ የቀረበው ውሳኔ ሀሳብ ለድምፅ ቀርቦ 503 ድግፍ ፣ 2 ድምጸ ተአቅቦና ያለምንም ተቃውሞ አንቀፁ ፀድቋል ።

ቀጥሎም ጉባኤው በአንቀጽ 27 ላይ ውይይቱን የቀጠለ ሲሆን በቅድሚያ የጉባኤው ምክትል ጸሐፊ አንቀጹን ለቤቱ በንባብ ከአሰሙ በኋላ የጉባኤው ሊቀመንበር በአንቀጹ ላይ ማሻሻያ ወይም አስተያየት ካለ መቅረብ እንደሚቻል ገልጸዋል ።

በዚህም መሠረት አቶ ሸምሰዲን አህመድ ከክልል 5 የእስልምና ሆነ የክርስትና ሃይማኖት ተከታዮች ሃይማኖቶቻቸውን ማራመጃና ማስፋፊያ ድርጅቶች እንዳሏቸው ጠቀመው የሃይማኖት ማስፋፊያ ማራመጃ ተቋማትን የማቋቋም መብት በአንቀጽ 27 ንዑስ አንቀጽ 1 ላይ በግልጽ ስላልተመጠ ከንዑስ አንቀጹ መጨረሻ " ማንኛው ሰው እምነቱን ለማራመድ ከሌሎች ጋር በመሆን በሕግ በሚፈቀደው መሠረት የሃይማኖት ተቋም የማቋቋም መብት አለው ። " የሚል ዐረፍተ ነገር እንዲገባ ሀሳብ ያቀረቡ ሲሆን ይህም አሁን ያሉትን የሃይማኖት ተቋማት ሕጋዊነት ከማረጋገጡም ሌላ ሃይማኖት ተከታዮች ከመሰሎቻቸው ጋር በዓለም አቀፍ የሚገናኙበትን መድረክ እንደሚፈጠር አመልክተዋል ።

በማስከተልም አቶ አብዲ ጃማ ደብሌ ከክልል 5 በቀደምት ሥርዓቶች በተለይ የእስልምና ሃይማኖት ተከታዮች በዓላቸውን እንዳያከብሩ ከሌሎች አገሮች የሃይማኖቱ ተከታዮች ጋር ግንኙነት እንዳያደርጉ ሲታፈኑ እንደነበር ፣ እንደአዲስ አበባ ባሉት ትላልቅ ከተሞች ከመስጊድ ብዛት ማነስ የተነሳ በከተማይቱ ያሉት እስላሞች በተለይ ዓርብ ዓርብ ዕለት የመስገጃ ቦታ በማጣት መቸገራቸው የዚሁ ተፅዕኖ ውጤት መሆኑን ፣ የእስልምና ሃይማኖት ትምህርት ቤቶችን በማቋቋም በኩል የነበሩት ቀደምት ሥርዓቶች ትኩረት እንዳልተሰጠው አስረድተው የብሔር/ብሔረሰቦችና ሃይማኖቶች እኩልነት በተረጋገጠበት በአሁኑ ወቅት ግን የሃይማኖት ተቋማትና ትምህርት ቤቶችን ማቋቋም ከፍተኛ ትኩረት እንዲሰጠው እንዲሁም የሃይማኖት ተከታዮቹ ከዓለም እስላም ኅብረተሰብ ጋር ግንኙነት የሚፈጥሩበት ሁኔታዎች እንዲመቻቹ አሳስበዋል ።

አንድ የጉባኤው አባል ደግሞ የኢትዮጵያ ብሔር / ብሔረሰቦች ተወካዮች በየራሳቸው ቋንቋ ሀሳባቸውን እየገለጹ በእኩልነት ሲገኙ የሕገ መንግሥት ጉባኤ



በታሪክ የመጀመሪያው እንደሆነና ታላቅ ደስታ እንደፈጠረላቸው ፣ ይህንን እኩልነት ለማስገኘት ሲሉ የወደቁ አባቶች ከመቃብር ተነስተው ቢያዩት ኖሮ የዛሬው ደስታቸው እጥፍ ድርብ ይሆን እንደነበር ገልጸው በአሁኑ ጊዜ ያለው የብሔር /ብሔረሰቦች ፍቅርና አንድነት ለማመልከት የጉባኤው አባላት እርስ በርሳቸው እንዲሳሳሙ ጋብዘዋል ።

አያይዘውም በደርግ ጊዜ ሮቤ ከተማ ውስጥ የእስልምና ሃይማኖት ተከታዮች ተጨፍጭፈው መስጊዳቸው ፈርሶ እንደነበር ፣ ዛሬ ግን የፈረሰውን መስጊዳቸውን ሠርተው 2000 ያህል ተማሪዎች እየተማሩ እንደሆነና እግዚአብሔር ሊመሰገን እንደሚገባው ገልጸው መስጊዱን ያስፈረሰውና የሃይማኖት ተከታዮችን ያስጨፈጨፈው ክብረት ጎንጤ አስከሬኑ አሞራ እንደበላው ተናግረዋል ።

በሌላ በኩል አቶ መሐመድ ቢን መሐመድ ከክልል 3 በአፄ ኃይለሥላሴ ዘመነ መንግሥት ከኦርቶዶክስ ሃይማኖት ተከታዮች በስተቀር የሌሎች ሃይማኖት ተከታዮች ትምህርት ቤት ለመማር ሆነ በመንግሥት መሥሪያ ቤቶች እንዳይሠሩ ተፅዕኖ ይደረግባቸው እንደነበር ፣ በተለይ እስላም ከሆነ ለመማርም ሆነ በመንግሥት መሥሪያ ቤቶች ለመስማራት ስሙን እንዲቀይር ጥያቄ ይቀርብለት እንደነበር ፣ ጥያቄውን ካልተቀበለም ከትምህርት ቤት ወይም የመንግሥት መሥሪያ ቤት እንደሚበረር ገልጸው አንቀጽ 27 የሃይማኖቶች ነፃነት የሚያጎናጽፍ በመሆኑ እንዳለ እንዲፀድቅ ሀሳብ አቅርበው በተጨማሪም የአርባጉጉ ተወላጆች በትምህርት ወደኋላ የቀሩት ለመማር ባለመፈለጋቸው ሳይሆን በሃይማኖት ምክንያት በሚደርስባቸው ተፅዕኖ እንደሆነ አመልክተዋል ።

ቀጥሎም አቶ ደመቀ መኮንን ከክልል 3 የሃይማኖት ተቋማትን ማደራጀት የመብት በአንቀጽ 27 ንዑስ አንቀጽ 1 እንዲካተት በአቶ ሸምሰዲን አህመድ ከክልል 5 ከቀረበው ሀሳብ በመነሳት በሰጡት አስተያየት የሃይማኖት ተቋማትን የመደራጀት መብት ቤቱ በአንቀጽ 31 ላይ ሲወያይ ሊነሳ እንደሚችል ፣ አንቀጽ 27 ንዑስ አንቀጽ 1ም ቢሆን አንድ ሰው የፈለገውን እምነት የመያዝና የመግለጽ መብት እስከ ፈቀደ ድረስ እምነቱን በቤተክርስትያን ወይም በሌላ የሃይማኖት ተቋም የማራመድ መብቱን እንደማይከለክለው ገልጸዋል ።

በሌላ በኩልም አንድ የጉባኤ አባል በበኩላቸው በአንቀጽ 27 ንዑስ አንቀጽ 1 ላይ የተቀመጠው የሃይማኖት ትምህርት በግል ማስተማርን ብቻ የሚመለከት በመሆኑና የእስልምና ትምህርት በኢትዮጵያ የሚሰራጨው ደግሞ በግል ማስተማር ብቻ ሳይሆን በሃይማኖት ማስተማሪያ ተቋማት አማካይነት እንደሆነ ጠቅሰው የሃይማኖት ተቋማት የመደራጀት መብት በአንቀጹ እንዲካተት አሳስበው ይህ

J00100

::

...ተብሎ የቀረበው ሀሳብ አንቀጹ የሥልጣኔ
መብት በአንቀጽ 31 ሊጠቃለል ይችላል አስፈድቶዋል ::
ድርጅቶችን የሚያመለክት በመሆኑ ሀሳቡ እንደማይስከድ ... ዘመትር ዓርብ ዓርብ
ከዚያም አቶ ታረቀ ፅጊ ከክልል 14 በአሁኑ ጊዜ ... ወደአንዋር መስጊድ የሚያመሩ
በእስልምና ሃይማኖት ተከታዮች መስገጃ ሰዓት ... ሃይማኖት ባለቤት ምርዓቶች
የአዲስ አበባ መንገዶች ዝግ እንደሚሆኑ አስታውሰው ... ዲሞክራሲያዊ መንግሥት
ከፍተኛ በደል የደረሰበት በመሆኑ ወደፊት የሚቋቋመው ... ማሰሪያ ቦታ በመስጠት
የሃይማኖት ተቋማትን በማስፋፋት በኩል የመስጊድ ... ሃይማኖት ልዩ ትኩረት
እንዲሁም የማትሪያልና የሞራል እገዛ በማድረግ ለእስልምና ... እንደሚቀበሉት ገልጸዋል ::
ሊሰጥ እንደሚገባ ጠቅሰው የቀረበውን የማሻሻያ ሀሳቡም ... ሃይማኖት ተከታዮች
ከዚያም የጉባኤው ፀሐፊ በኢትዮጵያ የእስልምና ... አካባቢ እንዳይኖሩ
ስማቸውን እንዲቀይሩና በአንዳንድ ክርስትያኖች በሚኖሩበት ... አውስተው ጉባኤው
ተፅዕኖ ከመደረጉም በላይ አንድ ሰው ከከዳ ስለመ እንደሚባል ... ለሚቀጥለው ስብሰባ
ጉዳዩ ከአንቀጽ 17 ጋር የበለጠ በጥልቀት እንዲያየው ...
እንዲተላለፍ ያቀረቡት ሀሳብ ተቀባይነት አግኝቷል ::
የጉባኤው ሊቀመንበር ስለ ሕገ መንግሥቱ አረቃቀቅ የተለያዩ አካላት
አስተያየታቸውን መስጠት እንደሚችሉ በዜና ማሰራጫዎች በተገለጸው መሠረት
አስተያየታቸውን መስጠት የሚፈልጉ ግለሰቦች የሚያቀርቡትን ሀሳብ ለማዳመጥ
የሚፈልግ የጉባኤው አባል 9.00 ሰዓት አዳራሹ ድረስ መምጣት እንደሚችል ገልጸው
ከሰዓት በኋላ ጉባኤው ውይይቱን እንደማይቀጥል አስታውቀው የዕለቱ የጉባኤው
ወይይት ከቀኑ 7.00 ተጠናቋል ::

J00101

ኅዳር 7 ቀን 1987 ዓ.ም ከጧቱ በ3፡05 ሰዓት በሕገ መንግሥት ጉባኤ አዳራሽ የተጀመረው የሕገ መንግሥት ጉባኤ ስብሰባ የተመራው በጉባኤው ሊቀመንበር ዶ/ር ነጋሶ ጊዳዳ ሲሆን በትድሚያ የጉባኤው ዋና ፀሐፊ አቶ አዲሱ ለገሠ በዕለቱ 521 የጉባኤ አባላት በመገኘታቸው ስብሰባውን መጀመር እንደሚቻል ከገለጹ በኋላ የጉባኤው ሊቀመንበር የዕለቱ ወይይት ባለፈው ዕለት ጉባኤው የጀመረውና በዕለቱ ውሳኔ ላይ ለመድረስ ባለመቻሉ ምክንያት በተላለፈው የሃይማኖት ፣ የእምነትና የአመለካት ነፃነት በሚለው አንቀጽ 27 እንደሆነ ጠቅሰው ጉዳዩን በተመለከተ የሰብአዊና ዲሞክራሲያዊ መብት ኮሚቴ የወሰዳቸው ግንዛቤዎችና የደረሰባቸው አዳዲስ የውሳኔ ሀሳቦች ካሉ በትድሚያ ለቤቱ ቢያቀርብ እንደሚጠቅም ገልጸዋል ::

በዚህም መሠረት የሰብአዊና ዲሞክራሲያዊ መብት ኮሚቴ ሰብሳቢ ወ/ሮ አረጋሽ አዳነ በሰጡት ማብራሪያ ጉባኤው ውይይቱን ያካሄደው ከዚህ ቀደም በነበሩ ሃይማኖትን ለማስፋፋት የሚረዱ የሃይማኖት ትምህርትና የአስተዳደር ተቋማት እንዳሉ ሆነው ለወደፊቱም እነዚህን ተቋማት ለማስፋፋት የሚቻልበትን መንገድ በአንቀጽ 27 ውስጥ ይካተት የሚለውን የጉባኤውን የጥያቄና የውይይት መንፈስ መሠረት በማድረግ እንደሆነ አመልክተዋል ::

አያይዘውም በውይይቱ ሂደትም ተቋማት የሚስፋፉበትን መንገድ ማካተት ያስፈልጋል የሚሉና አያስፈልግም የሚሉ ሀሳቦች እንደተንሸራሸሩና በመጨረሻ ግን በሕገ መንግሥቱ ቢካተቱም ባይካተቱም ጥንካሬያቸው ከሃይማኖት ሃይማኖት ቢለያይም በተጨባጭ ግን ያሉ መሆናቸውን የታወቀ በመሆኑና ለወደፊቱም ተመሳሳይ የሃይማኖት ትምህርት ቤቶች ፣ ፀሎት ቤቶችና የአስተዳደር ተቋማት የሚስፋፉበት ሁኔታ ቢካተት ችግር እንደሌለው ኮሚቴው ከስምምነት ላይ እንደደረሰና ለዚህም " በአንቀጽ 90 ንዑስ አንቀጽ 2 የተጠቀሰው እንደተጠበቀ ሆኖ የሃይማኖት ተከታዮች ሃይማኖታቸውን ለማስፋፋትና ለማደራጀት የሚያስችላቸው የሃይማኖት ትምህርትና የአስተዳደር ተቋማት ማቋቋም ይችላሉ :: " የሚል በንዑስ አንቀጽ 1 መጨረሻ ላይ እንዲታከል ለቤቱ ሀሳብ ማቅረቡን አስታውቀዋል :: ከዚያም የጉባኤው ሊቀመንበር በቀረበው የውሳኔ ሀሳብ ላይ ከቤቱ አስተያየት ካለ መቅረብ እንደሚቻል ገልጸዋል ::

በዚህም መሠረት አቶ ሸምሰዲን አህመድ ከክልል 5 በሰጡት አስተያየት በአንቀጽ 27 ንዑስ አንቀጽ 1 ላይ የተቀመጠውና የመረጡትን ሃይማኖት ወይም እምነት የመያዝ ፣ የመቀበል ፣ የማምለክ ፣ የመከተል ፣ የመተግበር ፣ የማስተማር

ወይም የመግለጽ መብት ምሉዕነት የሚኖረውና የሃይማኖት ሕልውና የሚረጋገጠው ከቤተሰብ ተነስቶ እስከ አገር አቀፍና ዓለም አቀፍ ድረስ በሚዘረጉት የሃይማኖት ተቋማቱ በመሆኑ እነዚህን ተቋሞች የማጠናከሩና አዳዲስም የመክፈትና የማስፋፋቱ መብት እንዲታከል ኮሚቴው ያቀረበው ሀሳብ ተገቢና ተቀባይነት ያለው እንደሆነ ገልጸው በኢትዮጵያ በክርስትና ሃይማኖት የሲኖደስ ፣ በእስልምና ደግሞ የእስልምና ጉዳዮች ከፍተኛ ጉባዔ ለተጠቀሱት ሃይማኖቶች በየበኩላቸው የሚሰጡት ጠቀሜታ ከማምለኩ የሚተናነስ ስላልሆነ ለወደፊቱም ተመሳሳይ ተቋማትን ማስፋፋት መቻሉ በሕገ መንግሥቱ መረጋገጡ አስፈላጊ እንደሆነ አመልክተዋል ::

ቀጥሎም አቶ ካሚል አህመድ ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል የኮሚቴውን የማሻሻያ ሀሳብ እንደሚቀበሉት ጠቁመው የሚቀበሉትም ሃይማኖቶች አስተዳደራዊ ተቋማትን ማስፋፋት እንደሚችሉ በመብት ከተረጋገጠላቸው ከዚህ ቀደም ሲካሄድ የነበረውን ሃይማኖቶችን የማበላለጥ ድርጊትን ሊያስወግድና በረቂቁ አንቀጽ 31 የተቀመጠውን ካልተፃረረ ለሃይማኖት ሆነ ለሌላ አላማ መደራጀት የመቻሉን መብት ተግባራዊ ሊያደርገው የሚችል እንደሆነ ገልጸዋል ::

ከዚያም አቶ አሊ አብዶ ከክልል 14 በበኩላቸው ባለፉት ሥርዓቶች በእስልምናና በሌሎች ሃይማኖቶች ላይ ግፍና በደል እንደተፈጸመ አስታውሰው በአሁኑ ጊዜ ግን ለሃይማኖቶች እኩል ዕውቅናና ክብር እየተሰጠ መሆኑን ጠቅሰው ለዚህም የክልል 14 መስተዳድር ባለፉት 3 ዓመታት ለእስልምና ጉዳዮች ከፍተኛ አክብሮት በመስጠትና የተቻለውን ያህልም ችግሮችን በጋራ ለመፍታት ጥረት ማድረጉን በምሳሌነት አቅርበው በኮሚቴው የቀረበው ሀሳብ በሃይማኖት ለመደራጀት የሚያስችል ፣ ሕገ መንግሥቱን የሚያዳብርና ሕዝቡም እንደሚረዳው የበኩሉን አስተዋፅኦ የሚያበረክት በመሆኑ ተገቢ እንደሆነ አስረድተዋል ::

አክለውም አቶ ዩሱፍ መሐመድ ከክልል 2 የእስልምና ሃይማኖት ይዘው የመጡትን የነብዩ መሐመድ መልዕክተኞች በጊዜው የነበሩት የኢትዮጵያ ነገሥታትና ሕዝቦች በደስታ እንደተቀበሏቸውና ሃይማኖቱንም እንዲሰብኩ እንደፈቀዱላቸው ፣ በክርስትናና በእስልምና ሃይማኖት ተከታዮች መካከልም ፍቅርና መከባበር እንደነበር ከጊዜ በኋላ ግን የገገር መደቦች የእስልምና ሃይማኖትን ዝቅ አድርገው በመመልከት በሃይማኖቱ ተከታዮች ላይ ጭቆና እንዳደረሱ ገልጸው የሽግግር መንግሥቱ ከተቋቋመ ወዲህ ለእስልምና ሃይማኖትና ለሌሎችም ከበሬታ በመስጠቱ ሁሉም ሃይማኖቱ የሚፈቅደውን በማደረግ ላይ እንደሚገኝ አመልክተዋል ::

አያይዘውም በተፈጠረላቸው አመቺ ሁኔታ ምክንያት ሃይማኖታቸው የሚፈቅደውን ማለትም መስጊድ መሥራት ፣ የሴቶች በሻሽ ራሳቸውን ሸፍነው



መሄድ ፣ ወዘተ... ለሃይማኖት መገዛት ሳይሆን እንደአክራሪነት እየተቆጠረ አክራሪ የነበሩት ሰዎች እንደነበሩ ጠቁመው ይህንን ድርጊት በሕገ መንግሥቱ የተረጋገጠው የሃይማኖት መብትና ተቋማትን ለማስፋፋት እንዲቻልም በኮሚቴው የቀረበው ሀሳብ ተቀባይነት ያለው መሆኑን ገልጸዋል ::

ቀጥሎም ቄስ ያለው ዘውዴ ከክልል 3 በበኩላቸው እግዚአብሔር ሰውን ሲፈጥር ሁሉን እኩል አድርጎ እንጂ አንተ እስላም ነህ ዝቅ በል ፣ አቶ ደግሞ ክርስቲያን ነህ ከፍ በል በማለት እንዳልሆነ ፣ ጌታ እግዚእነ ኢየሱስ ክርስቶስ ለሃይማኖት መምህራን ሲያስተምር ስለሃይማኖት አስተምሩ እንጂ በግድ ወደ ሃይማኖቱ ውሰዱ አለማለቱንና በአምሳሉ የፈጠረውን ሰውን ብቻ ሳይሆን አራዊትም ሳይቀር በቋንቋቸው ፈጣሪያቸውን እንሚያመሰግኑና እርስ በርሳቸው እንዲፋቀሩ ማዘዙን ገልጸው ባለፉት የከፋፍለህ ግዛው ሥርዓቶች ግን መንግሥት የሚከተለው የኦርቶዶክ ሃይማኖት ብቻ እየተከበረ በሌሎች ሃይማኖቶች ላይ ጭቆና መድረሱን በተለይም የእስልምና ሃይማኖት ተከታዮች የሚቀብሩበት መሬት ሳይቀር እየተከለከሉና የተለየ ጭንጫ መሬት እየተሰጣቸው ከዚያም ካለፈ በአስር ይሰቃዩ እንደነበር ፣ ፈላሻዎችም ሁሉም የሚገለገልበት ሸክላ ሠርተው ጉቦ መስጠት ይገደዱ እንደነበር አስታውሰው ይህን የሚያስወግድ መብትን የሚያረጋግጥ በመሆኑ እንደሚቀበሉት ገልጸዋል ::

ከዚያም የጉባኤው ሊቀመንበር ኮሚቴው ያቀረበውን ሀሳብ በመደገፍ አስተያየቶች መሰንዘራቸውን ገልጸው ከዚያ የተለየ ሀሳብ ካለ ሊቀርብ እንደሚችል ቢያሳስቡም የተለያ ወይም ተቃዋሚ ሀሳብ ባለመቅረቡ የኮሚቴው የውሳኔ ሀሳብ እንዲፀድቅ ለድምፅ አቅርበውት ድጋፍ 520 ፣ ድምፀ ተአቅቦ 4 ተመዝግቦ ያለ ምንም ተቃውሞ ፀድቋል ::

ቀጥሎም አንቀጽ 27 ከተደረገበት የኮሚቴው ማሻሻያ ጋር እንዲፀድቅ ለድምፅ ከመቅረቡ በፊት የተቃውሞ ሀሳብ ካለ አንድ ሰው ሊናገር እንደሚችል ባሳሰቡት መሠረት አቶ መሐመድ አህመድ ከክልል 3 ፣ በንዑስ አንቀጽ 4 "...ሃይማኖትን የመግለጽ መብት..." ከሚለው ውስጥ "የመግለጽ መብት" ሃይማኖት ማስፋፋትን ስለማያመለክትና በአለባበስ ፣ በንግግር ፣ ወዘተ... ሃይማኖትን መግለጽ ቢቻልም ማስፋፋትን ስለማይተካው ተቀይሮ የማስፋፋት መብት ቢባል እንደሚቻል ሀሳብ አቅርበዋል ::

ሆኖም በአንቀጽ 27 በተለይ በንዑስ አንቀጽ 1 ሃይማኖትን ከመግለጽ በላይ ተቋማትን ማስፋፋት እንደሚቻል ስለተገለጸ የተጠቀሰው ሥጋት ሊኖር እንደማይገባ የጉባኤው ዋና ፀሐፊ አቶ አዲሱ ለገሠ ገልጸዋል ።

የጉባኤው ሊቀመንበር የቃላቱን ጉዳይ ለሕገ መንግሥት ቀርጽ ኮሚቴ መተው እንደሚሻል አሳስበው ይህንንም አቶ መሐመድ አህመድ መቀበላቸውን ከገለጹ በኋላ አንቀጽ 27 ከነማሻሻያው እንዳለ እንዲፀድቅ ለድምፅ ቀርቦ ድጋፍ 525 ፣ ድምፀ ተአቅቦ 1 እና ያለምንም ተቃውሞ ፀድቋል ።

ከዚያም ውይይቱ "በሰብዕና ላይ ስለሚፈጸሙ ወንጀሎች" በሚለው አንቀጽ 28 ላይ የቀጠለ ሲሆን በቅድሚያ የጉባኤው ምክትል ፀሐፊ አቶ አባተ ኪሾ አንቀጹን ለቤቱ በንባብ ካሰሙ በኋላ የጉባኤው ሊቀመንበር አንቀጹን በተመለከተ የሰብአዊና ዲሞክራሲያዊ መብት ኮሚቴ ማብራሪያ ወይም የውሳኔ ሀሳብ ካለ ማቅረብ እንደሚቻል ገልጸዋል ።

በዚህም መሠረት የሰብአዊና የዲሞክራሲያዊ መብ ኮሚቴ ሰብሳቢ ወ/ሮ አረጋሽ አዳነ አንቀጹን በተመለከተ ጉባኤው ሲወያይ ከውስጥም ሆነ ከጉባኤው ውጭ ከሕግ ባለሙያዎችና ሌሎች አዋቂዎች የተለያዩ ሀሳቦችና አስተያየቶች ቀርበውለት እንደነበርና የቀረቡትንም ሀሳቦች መሠረት በማድረግ አንቀጹን የሚያጠናክሩ ማሻሻያዎችን ማድረጉን ገልጸዋል ።

በተደረገው ማሻሻያ መሠረትም አንቀጽ 28 ፦

" ኢትዮጵያ ባፀደቀቻቸው ዓለም አቀፍ ስምምነቶችና በሌሎች የኢትዮጵያ ሕጎች በሰው ልጅ ላይ የተፈጸሙ ወንጀሎች ተብለው የተጠቀሱትን ወንጀሎች፣ ኢሰብአዊ ድብደባዎች ፣ በአስገዳጅ ሰውን የመሰወር እርምጃዎች፣ ያለፍርድ የሞት ቅጣት እርምጃን መውሰድ ፣ በፈጸሙ ሰዎች ላይ ክስ ማቅረብ በይርጋ አይታገድም ። ይህ እንደተጠበቀ ሆኖ በዚህ አንቀጽ የሞት ቅጣት ለተፈጸመባቸው ሰዎች ርዕሰ ብሔሩ ቅጣቱን ወደዕድሜ ልክ እስራት ሊቀንሱት ይችላሉ ።."

ተብሎ እንዲቀመጥ ኮሚቴው የውሳኔ ሀሳብ ማቅረቡን ገልጸው "በሕግ አውጪው ክፍልም ሆነ በማንኛውም የመንግሥት አካል ውሳኔዎች በምህረት ውይም በይቅርታ አይታለፍም" በሚው ምትክ "በዚህ አንቀጽ መሠረት የሞት ቅጣት ለተፈረደባቸው ሰዎች ርዕሰ ብሔሩ ቅጣቱን ወደ ዕድሜ ልክ እስራት ሊቀንሱት ይችላሉ ።" የሚለው ሲጨመርም ርዕሰ ብሔሩ አንድ ደረጃ ቢያሻሽሉ ሁኔታውን እያዩ ውሳኔ ሊሰጡ የሚችሉበትን መንፈስ ስለሚያንፀባርቅ እንደሆነ አመልክተው ይህ ሲባል ግን



ሁሉንም የሞት ቅጣት ወደ ዕድሜ ልክ እስራት ያሻሽላሉ ማለት ሳይሆን ሁኔታውን አይተው ሊያሻሽሉ መቻላቸውን መጠቆም እንደሆነ አስረድተዋል ።

አክለውም የመጀመሪያው ዐረፍተ ነገርና ኮሚቴው በውስጡ እንዲገባ ያደረገው ሀሳብ ደግሞ የተጠቀሱትን ዓይነት ኢሰብአዊ ወንጀሎች የፈጸመ ሰው ሳይከሰስ 50 ወይም 100 ዓመት ቢቆይም በሕይወት እስከ አለ ድረስ ግን መከሰሱ በይርጋ እንደማይታገድ እንደሚያመለክት ጠቁመዋል ።

ከዚያም የጉባኤው ሊቀመንበር ኮሚቴው ያቀረበውን የውሳኔ ሀሳብ መነሻ በማድረግ ወይም በመቃወም ሀሳብ ማቅረብ እንደሚቻል ባሳሰቡት መሠረት አቶ ገርማ ብሩ ከክልል 4 ኮሚቴው ማሻሻያ ያደረገበትን መሠረታዊ ምክንያት እንዲያብራራ ጠይቀዋል ።

ቀጥሎም አቶ ዓለምሰገድ ገ/አምላክ ከክልል 1 በበኩላቸው የኮሚቴውን ማሻሻያ እንዳለ ተቀብለው "በሕግ አውጪው ክፍልም ... በይቅርታ አይታለፍም" የሚለው ግን ከሚወጣ እንዳለ ቢቀመጥና "በዚህ አንቀጽ መሠረት የሞት ቅጣት ለተፈረደባቸው ሰዎች ርዕሰ ብሔሩ ቅጣቱን ወደ ዕድሜ ልክ እስራት ሊቀንሱ ይችላሉ ። " የሚለው ቢቀጥል የጉዳዩ የተወሰነ ገጽታ የበለጠ ግልጽ እንደሚሆን አሳስበዋል ።

አስከትሎም አቶ ሙሉጌታ ገ/ሕይወት ከክልል 1 በሰብዕና ላይ የሚፈጸሙ ወንጀሎች የሚለው አንቀጽ 28 የሚያስቀምጠው በወንጀለኛው ክስ ማቅርብ በይርጋ እንደማይታገድና ወንጀሉም በይቅርታ ወይም በምህረት እንደማይታለፍ እንጂ በዝርዝር ሕግ ስለሚወጡት የቅጣት ዓይነቶችና ደረጃዎች እንዳልሆነ ፣ በዚህ ሁኔታ ርዕሰ ብሔሩ የሞት ቅጣቱን ወደ ዕድሜ ልክ እስራት ሊለውጡ እንደሚችሉ አመልክተው ኮሚቴው በዝርዝር ሕግ ማቃለያና ማክበጃ ደረጃዎች በአንቀጽ 28 እንዲገባ ያደረገበት አስፈላጊና ሕጋዊ ምክንያት ምን እንደሆነ እንዲብራራ ጠይቀዋል ።

በሌላ በኩል አቶ ተስፋዬ ሰዶና ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል "ኢሰብአዊ ድብደባዎች ፣ በአስገዳጅ ሰውን የመሰወር እርምጃዎች ፣ ያለ ፍርድ የሞት ቅጣት እርምጃዎችን መወሰድ" የሚሉት መጨመር በዝርዝር ሕግ የሚወጡትን በሕገ መንግሥቱ ማስገባት ስለሚሆን እንደማይቀበሉት ገልጸው ርዕሰ ብሔሩ የሞት ቅጣቱን ወደ ዕድሜ ልክ እስራት ሊቀንሱት መቻላቸውን ማስቀመጥም ኢሰብአዊ ወንጀሎች በይቅርታ ወይም በምህረት አይታለፉም የሚለውን መቃረን እንደሚሆን አመልክተዋል ።

ከዚያም የሰብአዊና ዲሞክራሲያዊ መብት ኮሚቴ ሰብሳቢ ወ/ሮ አሬጋሽ አዳነ በሕገ ማብራሪያ " በሕግ አውጪው ሆነ በማንኛውም የመንግሥት አካል ውሳኔዎች በምህረት ወይም በይቅርታ አይታለፉም ። " የሚለው እንዳለ እንዲቆይ የቀረበው ሀሳብ በረቂቱ ነገሩ የማሻሻያ ሀሳቡን ስለማይፃረር በኮሚቴው በሙሉ ተቀባይነት እንዳለው ገልጸዋል ።

አክለውም " ኢሰብአዊ ድብደባዎች፣ በአስገዳጅ ሰውን የመሰወር እርምጃዎች ፣ ያለ ፍርድ የሞት ቅጣት እርምጃዎችን መውሰድ " የሚለው ለምን እንደተጨመረ ሲገልጹም ምንም እንኳን ኢትዮጵያ ባፀደቀቻቸው ዓለም አቀፍ ስምምነቶችና ሌሎች የኢትዮጵያ ሕጎች ኮሚቴው የጨመራቸው ወንጀሎች መኖራቸው የታወቀ ቢሆንም የተጠቀሱት መሰል ወንጀሎች በስፋት በተፈጸመባት ኢትዮጵያ ግን ወንጀሎቹ በውስጠ ታዋቂ ብቻ እንዲታወቁ ከመተው ግልጽ አድርጎ ማስቀመጥ እንደሚጠቅም ኮሚቴው ከግምት ውስጥ በማስገባት እንደሆነ ፣ ወንጀሎቹ የታወቁና ቁልፍ ከመሆናቸው አንፃር በአንቀጹ ውስጥ ቢጨመሩ ለግልጽነቱ ከመርዳታቸውም በላይ እንደማያንዛዙትና ከእነዚህ ውጭ ሌላ ካልታከለ በስተቀር ዝርዝር ናቸው ማለት እንደማይቻል አስረድተዋል ።

አያይዘውም " ርዕሰ ብሔሩ የሞት ቅጣትን ወደ ዕድሜ ልክ እስራት ሊቀይሩ ይችላሉ " ተብሎ የተሻሻለው በዝርዝር ሕግ መውጣት ያለበት ነው ለተባለውም አንድ ደረጃ ብቻ ሊያሻሻሉ የሚችሉ መሆናቸውን ማስቀመጥ መዘርዘር ሳይሆን እንዲያውን ማሻሻል የት ደረጃ ድረስ ብቻ እንደሆነ በማመልከት ለጉዳዩ ክብደት እንደሚሰጠው አስገንዝበዋል ።

ከዚያም ሐጂ አብዱራህማን አብዱልቃድር ከክልል 13 በኃይለሥላሴና በደርግ ዘመናት ኢሰብአዊ የሆነ ወንጀል የቱን ያህል እንደተፈጸመ የታወቀ መሆኑንና በዚህ ረገድ ኮሚቴው አንቀጽ 28ን ሲመረምር የተለያዩ ምሁራንን ፣ ዓለም አቀፍ ሰብአዊ መብት ጠባቂዎችን ፣ የተለያዩ አዋቂዎችንና ግለሰቦችን ሀሳብ በመቀበል በአንቀጹ ላይ ማሻሻያ ያደረገ በመሆኑ ማሻሻያው እንደሚቀበሉት ገልጸዋል ።

አስከትሎም አቶ አህመዲን ኢብራሂም ከክልል 4 በበኩላቸው የመጀመሪያውን የኮሚቴውን መነሻ ሀሳብ እንዳለ ተቀብለው የርዕሰ ብሔሩ የማሻሻል ሥልጣን ግን "በሕግ አውጪው ክፍልም ሆነ በማንኛው የመንግሥት አካል ውሳኔዎች በምህረት ወይም በይቅርታ አይታለፉም ይህ እንደተጠበቀ ሆኖ በዚህ አንቀጽ መሠረት የሞት ቅጣት ለተፈረደባቸው ሰዎች ርዕሰ ብሔሩ ቅጣቱን ወደ ዕድሜ ልክ እስራት ሊቀይሩት ይችላሉ ። " የሚለው እንዳለ በማስቀመጥ የመንግሥት አካል





/ ርዕሰ ብሔሩ/ ሥልጣን ሰፋ እንዲል መደረጉ ወይም የርዕሰ ብሔሩን ጉዳይ ለዝርዝር ሕግ ትቶ የመጀመሪያውን ማስቀመጥ እንደሚሻል ገልጸው በመጀመሪያው በረቂቱ ነገር ምትክ የሁለተኛው ይግባ የተባለው የኮሚቴው ማሻሻያ እንደማያስኬድ አመልክተዋል ።

ከዚያም የኮሚቴው ሰብሳቢ "በሕግ አውጪውም ሆነ በማንኛውም የመንግሥት አካል ውሳኔዎች በምህረት ወይም በይቅርታ አይታለፉም ። " የሚለው እንዳለ ሆኖ "ይህ እንደተጠበቀ ሆኖ በዚህ አንቀጽ መሠረት የሞት ቅጣት ለተፈረደባቸው ሰዎች ርዕሰ ብሔሩ ቅጣቱን ወደ ዕድሜ ልክ እስራት ሊቀንሱት ይችላሉ ። " የሚለው ተጨምሮ ማለፉን ኮሚቴው እንደሚቀበለው በድጋሚ ገልጸዋል ።

ቀጥሎም አቶ ተስፋይ ሐጎስ ከክልል 1 በኮሚቴው ማሻሻያ ሀሳብ ላይ ተቃውሞ እንዳላቸው ገልጸው ተቃውሞአቸውም በመጀመሪያ ኢሰብአዊ ድብደባዎች /Torture/ ፣ በአስገዳጅ ሰውን የመሰወር እርምጃዎች / Forced Disappearance / እና ያለ ፍርድ የሞት ቅጣት እርምጃዎችን መውሰድ/Summary Execution / የሚሉት ወንጀሎች በአንቀጽ 28 ውስጥ እንዲገቡ ኮሚቴው መወሰኑንና ይህ ሲደረግ ግን የአማርኛ ቃላቱ የእንግሊዝኛውን ፅንሰ ሐሳብ በትክክል ያልተካው እንደሆነና ሌሎች ትናንሽ ወንጀሎችንም ያካትታል ከሚል ሥጋት እንደሆነ አስታውቀዋል ።

አክለውም ሌላው ተቃውሞአቸው ርዕሰ ብሔሩ የሞት ቅጣቱን እንዲያሻሽሉ በኮሚቴው የቀረበውን ሀሳብ በተመለከተ በኢትዮጵያ ውስጥ በስብዕና ላይ እጅግ ከባድ ወንጀሎች ስለተፈጸሙና ለወደፊቱ ተመሳሳይ ወንጀል እንዳይፈጸም በአገሪቱም ሆነ በአፍሪካ አህጉር ከተፈጸሙ አሰቃቂ ድርጊቶች መማር ስላለባቸው ብቻ ሳይሆን በስብዕና ላይ ከሚፈጸሙ ወንጀሎች የበለጠ ወንጀል ባለመኖሩ ጭምር በእነዚህ ወንጀሎች ላይ የሚቀርበው ክስና የሚፈጸመው ቅጣት ምንም ዓይነት መሻሻል ሊደረግበት ስለማይገባው ከዚህ አኳያ ርዕሰ ብሔሩ የሞት ቅጣቱን ወደ ዕድሜ ልክ እስራት ሊለውጡ እንዲችሉ ኮሚቴው ማሻሻያ ማቅረቡን ተገቢ እንዳልሆነ አብራርተዋል ።

አያይዘውም በአንቀጽ 15 ማንኛውም ሰው በሕግ በተደነገገ ከባድ የወንጀል ቅጣት ሕይወቱን ሊያጣ እንደሚችል ተደንግጎ የታለፈ ስለሆነ በስብዕና ላይ ከሚፈጸሙ ወንጀሎች የበለጠ ከባድ ወንጀልም ስለሌለ ቅጣቱን የማሻሻል አስፈላጊነት እንደማያረካቸው አመልክተዋል ።

ቀጥሎም አቶ ተስፋዬ ፊቻላ ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል በሕገ መንግሥቱ አንቀጽ 71 ንዑስ አንቀጽ 6 ላይ ርዕሰ ብሔሩ በሕግ መሠረት ይቅርታ እንደሚያደርጉ መቀመጡን ለቤቱ ኢንፎርሜሽን ሰጥተው የሚፀድቀው ሕገ መንግሥቱ ዘመናዊ ፣ ርዕሰ ብሔሩ የሚመረጡትም በሚፀድቀው ሕገ መንግሥት መሠረት አገሪቱ ስታምንባቸው እስከሆነ ድረስ የፍርድ ቤት ውሳኔዎች እንደገና የማየት መለስተኛ ሥልጣን ቢሰጣቸው ችግር እንደሌለበት ገልጸዋል ::

ከዚያም የጉባኤው ዋና ፀሐፊ አቶ አዲሱ ለገሠ ሆኖም በሪፐብሊኩ ፕሬዚዳንት ሥልጣንና ተግባር ሥር የሚገኘው አንቀጽ 71 ንዑስ አንቀጽ 6 የሚመለከተው ከሞት ቅጣት በታች ያሉትን ሌሎች ቅጣቶች ሁሉ ሊጨምር የሚችል እንደሆነና ከእነዚህም መካከል የ10 ዓመት እስራት ወደ 5 ዓመት እስራት መቀየር ሊሆን እንደሚችል አመልክተው አንቀጽ 28 ግን በስብዕና ላይ ስለሚፈጸም ወንጀልና ቅጣቱም የመጨረሻው ማለትም የሞት ቅጣት በመሆኑ ለየት ባለ ሁኔታ መታየት ያለበት ስለሆነ በአንቀጽ 71 ከተቀመጠው እንደሚለይና የቀረበው ኢንፎርሜሽን ለቤቱ እንደማይረዳ አስገንዝበዋል ::

በማስከተልም አቶ አበበ ጎበና ከክልል 6 ርዕሰ ብሔሩ የሞት ቅጣቱን ወደ ዕድሜ ልክ እስራት ሊቀይሩ ይችላሉ ከሚለው በስተቀር ሌላውን የኮሚቴው ማሻሻያ እንደሚቀበሉት ገልጸው የሞት ቅጣት ከሆነ የሚያፀድቁት ርዕሰ ብሔሩ መሆናቸው የታወቀና ይህም በአንቀጽ 71 ላይ የተቀመጠው እንደሚበቃ ጠቅሰዋል ::

አክለውም ባለፈው የጉሙዝና የሺናሻ ሕዝቦች በማነሳሳት እስጨፍጭፋችኋል የተባሉ ሰዎች መስከረም 10 ቀን 1986 ዓ. ም ከተያዙ በኋላ መስከረም 12 ቀን 1986 ከእስር ቤት እየወጡ እንደተረሸኑ ፣ የቀሩት 22 የሺናሻ ማህበረሰብ አባላት በዕቃ ማከማቻ /ኮንቴኔር / ውስጥ በፓዌ በረሃ ለ7 ወራት ታስረው በደረሰባቸው ስቃይ መልካቸው ከተለወጠና የሞቱትም ከሞቱ በኋላ ከማዕከላዊ መንግሥት 3 ዳኞች ተልከው ሲያጣሩ ሰዎቹ አንድም ጥፋት አለመሥራታቸውና ምርመራ ያልተካሄደ መሆኑን ማረጋገጣቸውን ፣ በዚህም ምክንያት ምርመራው እንደገና ይጣራ በሚል አሁንም በእስር ቤት በመማቀቅ ላይ እንደሚገኙ ገልጸው ይህ የተደረገው በመጨረሻ በደርጋ አያስከስስም ከማለት ሊሆን ይችላል የሚል ፍራቻ ስላላቸው ርዕሰ ብሔሩ የሞት ቅጣቱን ሊያሻሽሉት ይችላሉ የሚለውን እንደሚቃወሙት አስታውቀዋል ::

በሌላ በኩል ደግሞ የጉባኤው ዋና ፀሐፊ አቶ አዲሱ ለገሠ ጥቅም የሚያሳድዱ ያለፈው ሥርዓት ናፋቂዎች በተለያዩ ብሔር /ብሔረሰቦች መካከል በጫሩት ጠብ ምክንያት በርግጥ በተጠቀሰው አካባቢ እንዲጨፋጨፉ ከተደረጉት ከሁሉም ብሔር/ብሔረሰቦች በኩል በርካታ ጭቁን ሕዝቦች መተላለቃቸውንና በከንቱ ሕይወት



መጥፋቱን ፣ የማዕከላዊ መንግሥት በአዋጅ በተሰጠው ሥልጣን መሠረት ችግሩን ለመፍታት በወሰደው እርምጃ ችግሩ በወቅቱ ተፈትቶ በሕግ የሚጠየቀውም እንዲጠየቅ ተደርጎ በአሁኑ ሰዓት በአካባቢው ሰላም መስፈኑን ገልጸው ጉዳዩ በሕግ ሂደት ገብቶ ባለበት በአሁኑ ሰዓት ከአንቀጽ 28 ጋር አስደግፎ ማቅረቡ አስቸጋሪ እንደሆነ ጠቅሰው በተረፈ ግን በአንቀጹ ላይ የሚጨመር ወይም የሚቀነስ ካለ ማቅረብ የማንም የጉባኤ አባል መብት መሆኑን የታወቀ እንደሆነ አመልክተዋል ::

ከዚያም ወ/ሮ አረጋሽ አዳነ የቀረበው የኮሚቴው ማሻሻያ ሀሳብ በአንቀጽ 28 ንዑስ አንቀጽ 1 ከተቀመጠው ርዕሰ ብሔሩ ማንኛው ዓይነት ቅጣት ይቅርታ ሊያደርጉ እንደሚችል ከሚደነግገው ጋር ተመሳስሎ መታየቱ ተገቢ እንዳልሆነ፣ በአንቀጽ 28 የተጨመረው ለየት ላለ ሁኔታ ማለትም በሰብዕና ላይ ወንጀል ተፈጽሞ ፍርዱ የሞት ቅጣት ከሆነ አንድ ደረጃ ማለትም ወደ ዕድሜ ልክ እስራት ብቻ ሊቀይሩ የሚችሉ መሆናቸውን የሚያስቀምጥ መሆኑ ታውቆ የቤቱ ውይይት ከዚህ አኳያ እንዲቀጥል አሳስበዋል ::

ቀጥሎም የጉባኤው ሊቀመንበር እስከ አሁን ድረስ የኮሚቴው ሁለተኛው ማሻሻያ ማለትም ርዕሰ ብሔሩ የሞት ቅጣትን ወደ ዕድሜ ልክ እስራት ሊቀይሩ እንደሚችሉ የቀረበውን የውሳኔ ሀሳብ በመቃወም አስተያየቶች መቅረባቸውን አመልክተው ከዚህ የተለየ ወይም አዲስ ሀሳብ ካለ ሊቀርብ እንደሚችል ገልጸዋል ::

በዚህም መሠረት ዶ/ር ሙክታር ረሺድ ከክልል 4 በሰነዘሩት አስተያየት በአንቀጽ 28 የተቀመጠው ደርጋ እንደ ወንጀሉ ዓይነት ከአገር አገር የሚለያይ እንደሆነ ፣ ኮሚቴው ባቀረበው ማሻሻያ "ኢሰብአዊ ድብደባዎች ፣ በአስገዳጅ ሰውን የመሰወር እርምጃዎች ፣ ያለ ፍርድ የሞት ቅጣት እርምጃዎችን መውሰድ" ወንጀሎች ክስ በደርጋ እንደማይታገድ መቀመጡን ሆኖም ከእነዚህ መካከል በአስገዳጅ ሰውን የመሰወር እርምጃዎችም በደርጋ እንደማይታገዱ መጨመሩ ተገቢ እንዳልሆነ ፣ ለምሳሌ ሰውን ፈንክቶ የምናሰውረውና ሌላ ከባድ ወንጀል ፈጽሞ የምናሰውረው ወንጀለኛ ተለይቶ መታየት እንደሚገባው አሳስበው ሰውን የማሰወር ወንጀል ከሕይወት ማጥፋት ወንጀል ጋር እኩል መታየት እንደማይገባ የጠቆሙ ሲሆን ርዕሰ ብሔሩ የሞት ቅጣቱን ወደ ዕድሜ ልክ እስራት ሊቀይሩ ይችላሉ የተባለውን ግን እንደሚቀበሉት ገልጸዋል ::

ቀጥሎም አቶ አበራ ዮሴፍ ከክልል 4 በደርጋ እንዳይታገዱ በሚል ኮሚቴው በአንቀጽ 28 ላይ እንዲጨመሩ ያላቸው "ኢሰብአዊ ድብደባዎች ፣ በአስገዳጅ ሰውን የመሰወር እርምጃዎች ፣ ያለ ፍርድ የሞት ቅጣት እርምጃዎችን መውሰድ" ወንጀሎች ተገቢ መሆናቸውን ገልጸው ዘርን የማጥፋት ፣ ሰውን በጅምላ የማሳደድና

የመሳሰሉት በስብዕና ላይ የተፈጸሙ ወንጀሎች የተፈጸሙበት ጊዜ ቢርቅም ሆነ ወንጀል ፈጻሚው ከአካባቢው ቢጠፋ ክሱ ግን በይርጋ አለመታገዱ ፣ በማንኛውም ባለሥልጣን ወይም የመንግሥት አካል በምህረት ወይም በይቅርታ አለመታለፉ አስፈላጊ እንደሆነ ጠቅሰው ርዕሰ ብሔሩ የሞት ቅጣቱን ወደ ዕድሜ ልክ እስራት ሊቀይሩ እንዲችሉ የተጨመረው ግን በስብዕና ላይ ከሚፈጸሙ ወንጀሎች የከበደ ወንጀል ካለመኖሩ አኳያ ምህረት ወይም ይቅርታ ስለማያስፈልግና ርዕሰ ብሔሩም በሕግ መሠረት የሌሎች ወንጀሎችን ቅጣቶች ሊያሻሽሉ የመቻላቸው ሥልጣን በአንቀጽ 71 የተቀመጠው ስለሚበቃ የኮሚቴው ማሻሻያ እንደሚቃወሙት አመልክተዋል ::

ከዚያም የጉባኤው ሊቀመንበር ኮሚቴው ያቀረበውን መሻሻያ በሚመለከት ተመሳሳይ የተቃውሞ ሀሳቦች መሰንዘራቸውን ጠቁመው ከቀረቡት ሀሳቦች የተለየ ተቃውሞ ካለ ሊቀርብ እንደሚችል ገልጸዋል ::

በዚህም መሠረት አቶ ደጉ ጨዕመ ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል በሰነዘሩት አስተያየት በኮሚቴው የተጨመሩት ኢሰብአዊ ድብደባዎች ፣ በአስገዳጅ ሰውን የመሰወር እርምጃዎች ፣ ያለ ፍርድ የሞት ቅጣት እርምጃዎችን መውሰድ ወንጀሎች ሴት ልጅን መጥለፍ ፣ የአባትን ደም መበቀልንና የመሳሰሉትን በርካታ ወንጀሎች የሚያካትት ስለሆነ በሕገ መንግሥቱ ለመዘርዘር ከመሞከር ለሕግ መተው እንደሚሻል ጠቅሰዋል ::

ቀጥሎም የጉባኤው ሊቀመንበር ቤቱ በአንቀጹ ላይ በቂ ውይይት ስለአካሄደበት ወደ ውሳኔ እንዲሸጋገር ሀሳብ ቢያቀርቡም እስከ አሁን የቀረቡት ግን የተቃውሞ ሀሳቦች ብቻ በመሆናቸው የድጋፍ ሀሳቦችም ካሉ እንዲቀርቡ ከውሳኔው በፊት ዕድል እንዲሰጥ የኮሚቴው ሰብሳቢ ወ/ሮ አረጋሽ አዳነ አሳስበዋል ::

ከዚያም የጉባኤው ሊቀመንበር ማሳሰቢያውን ተቀብለው የኮሚቴው ሀሳብ ከሚደግፉት አንድ ሰው ፣ ከተቃዋሚ አንድ ሰው እንዲናገሩ በያሳሰቡም በርዕሰ ጉዳዩ ላይ ሰፋ ያለ ማብራሪያ ከማስፈለጉና ቤቱም ተግባብቶና ተማምኖ የሚወስንባቸው ተቀራራቢ ሀሳቦች ከማስፈለጋቸው አንፃር አስተያየት የመስጠቱ ዕድል በሁለት ሰዎች ብቻ ሳይወሰን ተጨማሪ ዕድሎች ተሰጥተው ጉዳዩ የበለጠ እንዲብላላ እንዲደረግ አቶ ሀሰን አሊ ከክልል 4 የውሳኔ ሀሳብ አቅርበው የውሳኔ ሀሳቡ ከ1/3ኛ በላይ በቤቱ በመደገፉ ውይይቱ እንዲቀጥል ተወስኗል ::

በዚህም መሠረት አቶ ኩማ ደመቅሳ ከክልል 4 በሰጡት አስተያየት በኮሚቴው የቀረበውን ማሻሻያን በተመለከተ የተቃውሞ ሀሳቦች ሲሰነዘሩ በኮሚቴው የቀረቡት ጉዳዮች በተሳሳተ መንገድ የተሰጡ አስተያየቶች እንደነበሩ ፣ ከእነዚህም መካከል



ሰውን ፈንክቶ የመሰወር ተራ ወንጀል እስከ ሕይወት ማጥፋት ከሚደርሰው ሰውን አስገድዶ በመሰወር በስብዕና ላይ ከሚፈጸም ወንጀል ጋር ተመሳስሎ እንደቀረበ ፣ ሆኖም ኢሰብአዊ ድብደባዎች ፣ በማስገደድ ሰውን የመሰወር እርምጃዎች ፣ ያለ ፍርድ የሞት ቅጣት እርምጃን የመውሰድ ወንጀሎች ከባድ ወንጀሎች በመሆናቸው በይርጋ እንዳይታገዱ ኮሚቴው በአንቀጽ 28 ውስጥ እንዲካተቱ ማድረጉ ተገቢ እንደሆነ አብራርተዋል ::

አያይዘውም የርዕሰ ብሔሩ ቅጣት የማቃለል ሥልጣን በአንቀጽ 71 ተቀምጧል የሚል መከራከሪያ በማቅረብና ርዕሰ ብሔሩም በስብዕና ላይ የሚፈጸሙ ወንጀሎችን ቅጣት ማቃለል አይገባውም ከማለት በኮሚቴው ሁለተኛ ማሻሻያ ላይ የቀረበውን ተቃውሞ አስመልክተው ሲያብራሩም በአንቀጽ 71 የተቀመጠው በልዩ ሁኔታ የሚታየውን በስብዕና ላይ የሚፈጸም የወንጀል ቅጣትን ማቃለል ሳይሆን ስለሌሎች ወንጀሎች ስለሆነ አንዱ ሌላውን እንደማይተካው ፣ በተጨማሪም ርዕሰ ብሔሩም ቢሆን የሞት ቅጣቱን ወደ ዕድሜ ልክ እስራት ብቻ ሊቀይሩት የሚችለት በሕገ መንግሥቱ በተቀመጠውና በሕግ መሠረት በመሆኑ ቀዳዳ ይከፍታል የሚለው ሥጋት ሊኖር እንደማይገባው አብራርተው ሁለተኛው የኮሚቴው ማሻሻያ አግባብነት ያለው መሆኑን አመልክተው በሕግ አውጪው ክፍልም ሆነ በማንኛው የመንግሥት አካል ውሳኔዎች በምህረት ወይም በይቅርታ አይታለፉም የሚለውም እንዳለ መቀመጥ እንደሚኖርበት አሳስበው የኮሚቴው ማሻሻያ ሙሉ በሙሉ እንደሚቀበሉት ገልጸዋል ::

ከዚያም አቶ ዓለምሰገድ ገ/አምላክ ከክልል 1 በኮሚቴው የተጨመሩት ማሻሻያዎች አስፈላጊ እንደሆኑና አስፈላጊነታቸውም በስብዕና ላይ የሚፈጸሙ ወንጀሎች ምን ምን ናቸው የሚለውን በቅድሚያ ማየት እንደሚገባ ጠቅሰዋል ::

አያይዘውም በሕገ መንግሥቱ ረቂቅ ማብራሪያ ገጽ 63 ላይ በግልጽ እንደተቀመጠው በስብዕና ላይ የሚፈጸሙ ወንጀሎች በርካታ መሆናቸውን ፣ ከእነዚህም መካከል የሌላ ሃይማኖት ተከታዮችን መፍጀት ለምሳሌ ክርስትያን ነኝ በሚል የእስልምና ሃይማኖት ተከታዮችን መግደል ፣ ከራስ ብሔር የተለዩ ብሔሮችን በመጥላት ለመፍጀት አቅዶ በሙሉ ወይም በከፊል ተግባራዊ ማድረግ ፣ አንድ ሕዝብ በሕዝብነቱ ሊከበር ሲገባው ሊያገኘው የሚገባውን ሰብአዊ እንክብካቤ በመከልከል በረሀብ እንዲሞት ማድረግና የመሳሰሉት በሃይማኖት ፣ በዘር ወይም በፖለቲካ ምክንያት ሰዎችን በጅምላ በስፋት የመፍጀትና የማሰቃየት ወንጀሎች ዋና ዋናዎቹ እንደሆኑ አስረድተዋል ::

አክለውም የሰብአዊና ዲሞክራሲያዊ ኮሚቴ በአንቀጽ 28 ላይ ማሻሻያ ሲያደርግ በስብዕና ላይ ከሚፈጸሙት ወንጀሎች መካከል ከዋና ዋናዎቹ ሦስቱን

ማለትም ኢሰብአዊ ድብደባዎች ፣ በማስገደድ ሰውን የመሰወር እርምጃዎች ፣ ያለፍርድ የሞት ቅጣት እርምጃዎችን መውሰድ ወንጀሎች የሚሉት መርጦ እንዳካተተ ጠቀመው ለምሳሌ ኢሰብአዊ ድብደባ በዘር ፣ በሃይማኖት ወይም በፖለቲካ ምክንያት ሊደረግ እንደሚይችል ፣ በሌላ በኩል ወንጀል የፈጸመ ሰው ወንጀሉን ለማውጣጣት የሚደረግ ድብደባ ከእነዚህ የተለየ እንደሆነ አመልክተዋል ::

አቶ ዓለምሰገድ ገ/አምላክ ማብራሪያቸውን በመቀጠል በኢትዮጵያ በሰብዕና ላይ በሚዘገንን ሁኔታ ወንጀሎች ከመፈጸማቸው አኳያ ክሳቸው በደርጋ እንዳይታገድ በአንቀጹ በዝርዝር መካተታቸው አስፈላጊና ጠቃሚ እንደሆነ ፣ በደርጋ እንዳይታገዱ የሚያስፈልግበት ምክንያትም ርዕሰ ብሔሮችና ከፍተኛ ባለሥልጣኖች በሌሎች ወንጀሎች ላይ የሚቀርብ ክስ ደርጋ ካለፈ እንዳይከሰሱ ወይም ክሱ እንዲራዘም ፣ በይቅርታ እንዲታለፍ ወዘተ... የማድረግ ሥልጣናቸውን ተጠቅመው በሰብዕና ላይ ወንጀል የፈጸሙ ሰዎችም ሳይከሰሱና ተገቢውን ፍርድ ሳያገኙ እንዲቀሩ እንዳይደረግ እንደሆነ አመልክተዋል ::

አከለውም በሕግ አውጪው ክፍልም ሆነ በማንኛው የመንግሥት አካል ውሳኔዎች በምህረት ወይም በይቅርታ እንደማይታለፉ ሲቀመጥ ወንጀሉን የፈጸመው ሰው ወንጀሉን የሚመጥን ፍርድ ከተፈረደበት በኋላ እንዳለ ተግባራዊ መሆን ያለበት መሆኑን ማመልከት እንደሆነ ፣ ለምሳሌ በሰብዕና ላይ ወንጀል የፈጸመ ሰው የዕድሜ ልክ እስራት ቢፈረድበትም ምንም ሳይቀንስ ወይም ምህረት ሳይደረግለት ተግባራዊ እንደሚሆን በአንቀጹ መጨረሻ ላይ ርዕሰ ብሔሩ ቅጣቱን ሊቀንስ ይችላል ሲባል ይህንን መሻር ሳይሆን ወንጀሎች ከሚያስከትሏቸው ቅጣቶች መካከል አንዱንና የመጨረሻውን የሞት ቅጣት መርጦ አንድ ደረጃ ብቻ በመቀነስ ወደ ዕድሜ ልክ እስራት ሊለውጥ የመቻሉ ሥልጣን እንደተሰጠውና ይህም ሲሆን መሻሻል አለበት ተብሎ የተቀመጠ ሲሆን ሁኔታውን ለማየት ከፈለገ ሊያሻሽለው ወይም ላያሻሽለው የሚችል መሆኑን ክፍት እንደሆነ አስረድተዋል ::

አቶ ዓለምሰገድ ገ/አምላክ በመጨረሻም ርዕሰ ብሔሩ የሞት ቅጣትን ወደ ዕድሜ ልክ እስራት ሊቀይር እንደሚችል ሥልጣን ሲሰጠው ወንጀሎች የሚገባቸውን ቅጣት ሳያገኙ እንዳይቀሩ ከመነጨ መንፈስ ሥልጣኑ እንዳይሰጠው ሀሳብ መቅረቡን አስታውሰው በዚህ ሁኔታም ቢሆን ወንጀለኞች ተመጣጣኝ ቅጣት ይሰጣቸዋል እንጂ ሳይቀጡ ይቅሩ ማለት ስላልሆነ ሥጋቱ ሊወገድ እንደሚገባ አሳሰበው በሰብዕና ላይ ሰፊ ወንጀሎች በተፈጸሙባት ኢትዮጵያ የሞት ቅጣት አንድ ደረጃ የማሻሻሉ በር ዝግ አድርጎ መተው ምናልባት ወደ 2000 ወይም 5000 የሚደርሱ ሰዎችን በሞት መቅጣት አስፈላጊ ሆኖ ቢገኝ ከጥቅሙና ከጉዳቱ የትኛው እንደሚያመዝን የማየትንና የማመዛዘን ዕድልን መዝጋት እንደሆነ አስረድተው ::



የኮሚቴው ማሻሻያም ይህን መንፈስ ተከትሎ የተደረገ ስለሆነ እንዳለ ቢቱ ቢያፀድቀው እንደሚጠቅም አሳስበዋል ::

ከዚያም የጉባኤው ሊቀመንበር ወደ ውሳኔ ማለፉ ያስፈልግ እንደሆነ ቤቱን ጠይቀው ከ1/3ኛ በላይ ድጋፍ በማግኘቱ የጉባኤው ዋና ፀሐፊ አቶ አዲሱ ለገሠ አንቀጽ 28 የውሳኔ ሀሳቡን እንደሚከተለው አቅርበዋል ፤

" ኢትዮጵያ ያፀደቀቻቸው ዓለም አቀፍ ስምምነቶችና በሌሎች የኢትዮጵያ ሕጎች በሰው ልጅ ላይ የተፈጸሙ ወንጀሎች ተብለው የተወሰኑ ወንጀሎችን ፤ ኢሰብአዊ ድብደባዎች ፣ በማስገደድ ሰውን የመሰወር እርምጃዎችና ያለ ፍርድ የሞት ቅጣት እርምጃዎችን የመውሰድ ወንጀሎች በፈጸሙ ሰዎች ላይ ክስ ማቅረብ በደርጋ አይታገድም :: በሕግ አውጪው ክፍልም ሆነ በማንኛው የመንግሥት አካል ውሳኔዎች በምህረት ወይም በይቅርታ አይታለፉም ::በዚህ አንቀጽ የተጠቀሰው እንደተጠበቀ ሆኖ የሞት ቅጣት የተፈረደባቸው ሰዎች ርዕሰ ብሔሩ ቅጣቱን ወደ ዕድሜ ልክ እስራት ሊያሻሽለው ይችላል ::"

የሚል መሆኑን በንባብ ያሰሙ ሲሆን የኸው የውሳኔ ሀሳብ ለድምፅ ቀርቦ በሙሉ ድምፅ ተደግፎ ፀድቋል ::

ቀጥሎም በዲሞክራሲያዊ መብቶች ሥር የሚገኘው "የአመለካከትና ሀሳብን በነፃ የመያዝና የመግለጽ መብት" በሚለው አንቀጽ 29 ላይ ጉባኤው ውይይቱን የቀጠለ ሲሆን በቅድሚያ የጉባኤው ምክትል ፀሐፊ አቶ አባተ ኪሾ አንቀጹን በንባብ ለቤቱ አሰምተዋል ::

ከዚያም የሰብአዊና ዲሞክራሲያዊ መብት ኮሚቴ ሰብሳቢ ወ/ሮ አረጋሽ አዳነ አንቀጹን በተመለከተ በሰጡት ማብራሪያ ፤

- በአንቀጽ 29 ንዑስ አንቀጽ 1 ማንኛውም ሰው ያለ ምንም ጣልቃገብነት በሆነ ጉዳይ ላይ የራሱና የግሉ የሆነ ከማንም የተለየ አመለካከት መያዝ እንደሚችል ያን አመለካከት በመያዙም የሚነሳበት ጥያቄ እንደማይኖር እንደሚያመለክት ፤
- በአንቀጽ 29 ንዑስ አንቀጽ 2 ደግሞ ማንኛውም ሰው የራሱና የግሉ አመለካከት መያዝ ብቻ ሳይሆን የተለያዩ ማሰራጫ ዘዴዎችን ተጠቅሞ የማስተላለፍ ፤ መረጃና ሀሳብም የመሰብሰብና የማሰራጨት ግለሰባዊ መብት እንዳለው እንደሚያስቀምጥ ፤
- በአንቀጽ 29 ንዑስ አንቀጽ 3 የፕሬስ ነፃ መሆን እንደሚያበስር ማለትም ቅድመ ምርመራ በማንኛውም መልኩ የተከለከለና ለሕዝብ ጥቅም ያለው መረጃ /ኢንፎርሜሽን / የማግኘት ዕድልም የተከፈተ መሆኑን እንደሚያረጋግጥ፣

- አንቀጽ 29 ንዑስ አንቀጽ 4ም በኢትዮጵያ የተፈጠረው የዲሞክራሲ ልምድ እንዲሰፋና እንዲያድግ ፣ ጥልቀት እያገኘ እንዲሄድ ፣ አመለካከቶች ነፃ ሆነው እንዲሸራሸሩና ሀሳቦች ነፃ ሆነው በግልጽ መድረክ እንዲወጡ ለማድረግ ፣ ለሚቋቋሙት የመንግሥት ሆነ ከዚያ ውጭ ላሉ የፕሬስ ተቋማት መንግሥት ጥበቃ የማድረግ ፣ ኢንፎርሜሽን እንዲያገኙ የመርዳትና ሌሎች ለአላማቸው አስፈላጊ የሆኑ አስተዳደራዊ ድጋፎችን የመስጠት ኃላፊነተ እንዳለበት እንደሚያመለክት ፣
- አንቀጽ 29 ንዑስ አንቀጽ 5 ደግሞ የመንግሥት ፕሬስ ከመንግሥት ውጭ ያሉ የድርጅቶች ፣ ቡድኖችና ግለሰቦች ሀሳቦችንም የማስተናገድ ፣ የማስተላለፍና የመግለጽ ኃላፊነት እንዳለበት እንደሚያስቀምጥ ፣

ባጭሩ ከ1-5 ያሉት የአንቀጽ 29 ንዑስ አንቀጾች የግለሰብን የአመለካከትና ሀሳብን የመግለጽ ነፃነት ብቻ ሳይሆን የፕሬስ ተቋማት ነፃ መሆንና መንግሥትም ከመንግሥት ፕሬስ ውጭ ያሉትን ፕሬሶች ተጠናክረው የሕዝቡን ሕሊና በማዳበር በኩል የሚያበረክቱት አስተዋፅኦ እንዲሰፋ አስፈላጊውን ድጋፍና ትብብር ሊያደርግላቸው የሚገባ መሆኑን ስለሚያስቀምጥ እንዳሉ መፅደቃቸው ኮሚቴው እንዳመነበት ገልጸዋል ::

በሌላ በኩል ንዑስ አንቀጽ 6 በረቂቁ የያዘው መንፈስ እንደተጠበቀ ሆኖ አንዳንድ ማስተካከያዎችን ኮሚቴው እንዳደረገ ጠቁመው ማስተካከያዎቹ የተደረጉትም በሕገ መንግሥቱ ረቂቅ ላይ ከምሁራንና ሊቃውንት የተሰጡ አስተያየቶችን በማጤን ፣ የሕግ አማካሪዎችንና ሌሎች ለጉዳዩ ይረዳሉ የተባሉ ሰዎችን በማወያየት በተገኘው ግንዛቤና ጥቆማ መሠረት እንደሆነ ገልጸው አንቀጹም፣

- አንቀጽ 29 ንዑስ አንቀጽ 6 "እነዚህ ገደብ ሊጣልባቸው የሚችለው የሀሳብና የመረጃ ማግኘት ነፃነት በአስተሳሰባዊ ይዘት እና ሊያስከትል በሚችለው አስተሳሰባዊ ውጤት ሊገታ አይገባውም በሚል መርህ ላይ ተመሥርተው የሚወጡ ሕጎች ብቻ ይሆናሉ :: የወጣቶችን ደህንነት ፣ የሰውን ክብርና መልካም ስም ለመጠበቅ ሲባል ሕጋዊ ገደቦች በእነዚህ መብቶች ላይ ሊደነገጉ ይችላሉ :: የጦርነት ቅስቀሳዎች እንዲሁም ሰብአዊ ክብርን የሚነኩ የአደባባይ መግለጫዎች በሕግ የሚከለከሉ ይሆናሉ :: ስለሆነም ማንኛውም ዜጋ ከላይ በተጠቀሱት መብቶች አጠቃቀም የሚጣሉ ሕጋዊ ገደቦች ጥሶ ከተገኘ በሕግ ተጠያቂ ይሆናል ::"

የሚል ሆኖ እንዲቀመጥ ኮሚቴው ከስምምነት ላይ መድረሱን አመልክተዋል ::



የተደረገውን ማሻሻያ አስመልክተው ሲያብራሩም ከ1-5 ባሉት ንዑሳን አንቀጾች የተጠቀሱት የፕሬስ ነፃነት መብቶች ሕጋዊ ገደብ እንደሚያስፈልጋቸውና ገደቡ ሲደረግም ፣

- ሀሳቡ ወይም የፕሬስ ውጤቱ በሚያመጣው አስተሳሰባዊ ይዘትና በሚያስከትለው አስተሳሰባዊ ውጤት ሳይሆን የሚያመጣው ተጨባጭ ውጤት እየታ በሕግ መሠረት መሆን እንደሚገባው ፣
- በሕዝብ ላይ ጥፋት ሲያመጡ ፣ በወጣቶች ላይ የሥነ አእምሮአዊ ይሁን የልማድ መበላሸት ሲያስከትሉ ፣ የፕሬስ ነፃነትን መሠረት በማድረግ የጦርነት ቅስቀሳዎች እንዲሁም ሰብአዊ ክብር የሚነኩ የአደባባይ መግለጫዎች ሲወጡ መሆኑን በማየት እንደሆነ አስረድተዋል ::

ቀጥሎም የጉባኤው ሊቀመንበር በአንቀጹ ላይ ጥያዎች ወይም አስተያየቶች ካሉ ማቅረብ እንደሚቻል ባሳሰቡት መሠረት አቶ አዳሙ ደገፉ ከክልል 14 በአንቀጽ 29 ላይ በኮሚቴው የተሰጠው ማብራሪያ ይዘትና በንዑስ አንቀጽ 6 ላይ የተደረገው ማሻሻያ በተለይ ከ3-5 ባሉት ንዑሳን አንቀጾች የተሰጠው የፕሬስ ነፃነትን ጨርሶ የሚያዳፍን ፣ የፕሬስ ሰዎች ዲሞክራሲያዊ መብቶች የሚያኮላሽ ፣ ከመጻፍ እንዲታቀቡ የሚያደርጋቸውና መቀመቅ የሚያስገባቸው እንደሆነ ፣ በአጠቃላይ ከመንግሥት ጋዜጦች በስተቀር ሌሎች ጋዜጦች ተሰፋ ቆርጠው ሊጽፉ ከማይችሉበት ደረጃ ላይ የሚያደርሳቸው መሆኑን ገልጸው ለጦርነት የሚያነሳሱትን ገደብ እንዲጣልባቸው ማድረግ ሲቻል ኮሚቴው ባሻሻለው መልክ እንዲቀመጥ ማድረጉ ተገቢ ስላልሆነ ማሻሻያው እንደማይቀበሉት አመልክተዋል ::

ከዚያም አለሙ ፎቼ ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል በአንቀጽ 29 የተካተቱት የአመለካከትና ሀሳብን በነፃ የመያዝና የመግለጽ መብቶች ከሰው ልጅ አመለካከትና ፍልስፍና ጋር የተያያዙና መሠረታዊ በመሆናቸው ከኮሚቴው ማሻሻያ ጋር ቤቱ በአፅንኦት ሊቀበላቸው እንደሚገባ ገልጸዋል ::

አያይዘውም የኢትዮጵያ ሕዝብ በታሪኩ ጫዋነትንና ሥነ ምግባርን የተላበሰ በመሆኑ የወደፊት ልጆቹም በሥነ ምግባር ተሟልተው እንዲገኙ ስለሚሻ የወጣቶችን ሥነ ምግባር ለመጠበቅ ሕገ መንግሥቱ ትልቅ ሥፍራ መስጠቱን ፣ ያለፈው የጦርነት ታሪክ ገጽታ ተወግዶ ሰላማዊ መንገድ ለመከተል እንዲቻል ጦርነትን የሚቀሰቅሱ ግለሰቦችና ቡድኖች ሕጋዊ ገደብ እንዲጣልባቸው በሕገ መንግሥቱ ትኩረት መስጠቱ በጠቅላላው የኢትዮጵያ ሕዝብ የሚፈልጋቸው አበይት ዓላማዎች

እንደሆኑ ገልጸው ለዚህም በንዑስ አንቀጽ 6 ላይ ኮሚቴው ያደረገውን መሻሻያ ቤቱ በአፅንኦት ሊቀበለው እንደሚገባ አሳስበዋል ::

አክለውም ባለፉት ሥርዓቶች የመንግሥት የመገናኛ ብዙሃን አጠቃቀም የብሔር/ብሔረሰቦችን ቋንቋዎች ፣ ባህሎች ሊያንፀባርቁ ያልቻሉበት ሁኔታ እንደነበር ፣ ለምሳሌ በኃይለሥላሴ ዘመነ መንግሥት በልጅነታቸው በአማርኛ የሚተላለፉት የትምህርት በሬድዮ ሲያዳምጡ ለምን በሀድይኛ ቋንቋ በሬድዮ እንደማይተላለፍ አባታቸውን ሲጠይቁ " ሀድይኛ ሬድዮ ይሰብራል" የሚል ምላሽ የተሰጣቸውን በምሬት እንደሚያስታውሱት ገልጸው ለወደፊቱም ይህ መቀጠል ስለማይኖርበት የሽግግር መንግሥቱ ከተቋቋመ ጊዜ ጀምሮ ብሔር /ብሔረሰቦችና ሕዝቦች ቋንቋቸውንና ባህላቸውን በመገናኛ ብዙሃን የማስተላለፍ መብት ተጠናክሮ እንዲቀጥል ንዑስ አንቀጽ 5 ተሻሽሎ "በመንግሥት ገንዘብ የሚካሄደው ወይም በመንግሥት ቁጥጥር ሥር ያለ መገናኛ ብዙሃን የተለያዩ አስተያየቶች ፣ ብሔር /ብሔረሰቦችንና ሕዝቦችን ለማስተናገድ በሚያስችለው ሁኔታ እንዲመራ ይደረጋል ::" ተብሎ እንዲቀመጥ ሀሳብ አቅርበዋል ::

አስከተለም ዳንኤል በላይነህ ከክልል 14 አስተያየታቸውን የሚያቀርቡት በንዑስ አንቀጽ 3 እና ንዑስ አንቀጽ 6 ላይ መሆኑን ጠቁመው የንዑስ አንቀጽ 3 ይዘት ሲታይ የፕሬስና የመገናኛ ብዙሃን ቅድሚያ ምርመራ እንደማይደረግባቸውና መረጃ /ኢንፎርሜሽን / የማግኘት ዕድልም እንዳላቸው የተቀመጠና ከመንግሥት ፕሬስ ውጭ ለሆኑት ሁሉ የተሰጠ ቢሆንም የግል ጋዜጦች ግን ከአዲስ አበባ ወጥተው እንዳይሄዱ ኬላ ላይ ስለሚታገዱ በጠቅላላ በኢትዮጵያ ክልል ለመንቀሳቀስ እንዳልቻሉ ፣ ኬላ ላይ እንዲታገዱ ኦፊሰላዊ ትዕዛዝ ባይሰጥም መታገዳቸው ግን እውነት መሆኑን ፣ ከመንግሥት ውጭ ያሉ ፕሬሶች በፈለጉበት ቦታ ተንቀሳቅሰው ውጤታቸውን ሊያሰራጩ እንዲችሉ በንዑስ አንቀጽ 3 ሥር ይህንን የሚያመለክት ንዑስ አንቀጽ እንዲታከልበት ሀሳብ አቅርበዋል ::

አክለውም ንዑስ አንቀጽ 6ን በተመለከተም በንዑስ አንቀጹ ላይ በፕሬስ ላይ ገደብ ማስቀመጥ ካስፈለገ ባህልን የማያሳድፉትን ለይቶ ማስቀመጥ ሲቻል ከ1-5 ባሉት ንዑስ አንቀጾች የተመጡትን መብቶች በሙሉ በሚያግድና ነፃ ጋዜጦች የመሰላቸውን ጽፈው ለሕዝብ የሚያስተላልፉበትን ሁኔታ በሚገታ መልኩ ንዑስ አንቀጽ 6 ማስቀመጡ ተገቢ እንዳልሆነና ይህ ከሚደረግ ከ1-5 ያሉትን ንዑስ አንቀጾች አለማስቀመጡ ልዩነት እንደሌለው ገልጸዋል ::

አያይዘውም መንግሥት ለሕዝብ ድብቅ ዓላማውን ለማራመድ ሲሞክር፣ ግለሰብም ስውር ዓላማውን በሕዝብ መካከል ለማካሄድ በሚጥርበት ጊዜ የሚጋልጡት



ነፃ ጋዜጦች መሆናቸውን ፣ በአሁኑ ሰዓት ሊላ ኢንፎርሜሽን አቅርባችኋል ፣ መንግሥትን ተዳፍራችኋል በሚል ሰበብ የነፃ ጋዜጦች አዘጋጆች በፍርድ ቤት እየተከሰሱና እየታሰሩ እንደሚገኙ ገልጸው ለወደፊቱ ይህ እንዳይደረግ ንዑስ አንቀጽ 6 ሙሉ በሙሉ መሰረዝ እንደሚኖርበት ፣ ከ1-5 ባሉት ንዑሳን አንቀጾች መብት መስጠትና በንዑስ አንቀጽ 6 ደግሞ እገዳ ማስቀመጥ እንደማይገባ አመልክተዋል ::

በሌላ በኩል ደግሞ አንድ የጉባኤ አባል በሐረር ፣ በድሬዳዋና በአለማያ ከተሞች የግል የፕሬስ ውጤቶች እንደሚገኙና ሕዝቡም እየገዛ በማንበብ ላይ መሆኑን ገልጸው የግል ጋዜጦች ከአዲስ አበባ አይወጡም ብለው አቶ ዳንኤል በላይነህ ያቀረቡት ኢንፎርሜሽን የተሳሳተ መሆኑን ተናግረዋል ::

ከዚያም የጉባኤው ዋና ጸሐፊ አቶ አዲሱ ለገሠ የግል ጋዜጦች በአዲስ አበባ ከተማ ብቻ የተወሰኑ ሳይሆኑ በክልል 3 እስከ ጎንደር ከተማ ድረስ እንደሚነበቡ ፣ ሕዝቡ በሰላም በሚኖርበት ሁኔታ በጎንደር ጦርነት አለ ፣ ከፊኝ የሚባል ጦር ተነስቷል ፣ የሚል የውሸት ዜናቸውን ይዘው ያልሆነ ነገር እንደሚሰብኩ ራሱ የጎንደር ሕዝብ እያነበበ እየታዘባቸው እንደሚገኝ ገልጸው አቶ ዳንኤል በላይነህ የግል ጋዜጦች ከአዲስ አበባ ከተማ አይወጡም ይበሉ እንጂ ወደ ክልል ሄደው ቢያዩ ማረጋገጫቸው እንደማያጠራጥር ጠቁመዋል ::

ከክልል 6 አንድ የጉባኤ አባልም የግል ጋዜጦች እሶሳ ጠረፍ ድረስ ደርሰው መነበባቸውን ጠቅሰው ለምሳሌ ሮሃ የሚባል ጋዜጣ የደርግ ኃይል ኩመርኩን እንደተቆጣጠረና በአካባቢው የሚገኘውን የኢሕአዴግ ሠራዊትና በድንበር ያለው ሠራዊት ቦታውን እንዲለቁ ተገደው ከተማዋን በሄሊኮፕተር በመቆጣጠር ላይ እንደሚገኝ የጻፈውን ወሬ ማንበቡን ፣ በመሆኑም የነፃ ጋዜጦች ከአዲስ አበባ አይወጡም ብሉ የተሳሳተ ኢንፎርሜሽን ከመስጠት በፊት እቦታው ሄዶ ማየትና ማረጋገጥ እንደሚሻል አሳስበዋል ::

አቶ ዳንኤል በላይነህ ከክልል 14 በበኩላቸው ወደ ክልሎች የግል ጋዜጦች አያልፉም ሳይሆን በድብቅ በኮንትሮባንድ መልክ እንደሚሄዱና ይህ የጋዜጦችን የኮንትሮባንድ ዕቃ መሆን እንዳሳሰባቸው ገልጸዋል ::

ቀጥሉም የጉባኤው ሊቀመንበር ደግሞ እርሳቸው በተዘዋወሩባቸው እንደ አምቦ ፣ ደብረብርሃን ፣ አዳማ ፣ ወሊሶ ባሉት ከተሞች የግል ጋዜጦች በግልጽ ሲያልፉና ሲነበቡ በዓይናቸው ማየታቸውን ገልጸው ጋዜጦች ለማለፍ ሲሞክሩ የተያዙበትን ትክክለኛ ቦታ መጠቆም እንጂ በጠቅላላው የተከለከሉ ናቸው ማለቱ ስህተት እንደሆነ ጠቅሰዋል ::

አስከትሎም የጉባኤው ምክትል ጸሐፊ አቶ አባተ ኪሾ በበኩላቸው የፕሬስ አዋጅ ከወጣ ወዲህ ጋዜጦች የግል ወይም የመንግሥት ተብለው ሳይለዩና ምንም ዓይነት እገዳ ሳይደረግባቸው በየትኛው ቦታ በመሸጥ ላይ ስለሚገኙ ከአዲስ አበባ አይወጡም የተባለው ውሸት እንደሆነ ገልጸው የተሳሳተ ኢንፎርሜሽን ለጉባኤው ማቅረብ አግባብ ስላልሆነና ኢንፎርሜሽኑም በተጨባጭ ተረጋግጦ እውነትነቱና ውሸትነቱ ተለይቶ ማስተላለፍ ስለሚገባ እገዳው የተካሄደበትን ኬላና ጊዜውን ፣ የታሰረው ጋዜጠኛም ማን እንደሆነና መቼ እንደታሰረ ተጨባጭ ማስረጃ ለቤቱ መቅረብ እንደሚኖርበት አሳስበው ይህ ካልተደረገ ግን በጋዜጦች የተጻፈውን ውሸት በአካል ሰምቶ እንዲሁ ማለፍ እንደሚሆን ጠቁመው በተረፈ ግን አንቀጽ 29 ንዑስ አንቀጽ 2 ማንኛውም ግለሰብ አመለካከቱን በአገር ውስጥም ሆነ በውጭ አገር በየትኛው ቦታ የፈለገውን የማስራጫ ዘዴ ተጠቅሞ ማስራጨት የሚችል መሆኑን በግልጽ እንዳስቀመጠ አስረድተዋል ፡፡

የጉባኤው ሊቀመንበር አቶ ዳንኤል ባይነህ ከክልል 14 ያቀረቡት ኢንፎርሜሽን ቤቱ ያልተቀበለው በመሆኑ የግል ጋዜጦች ከአዲስ አበባ ሲወጡ የታገዱበትን ትክክለኛ ቦታ /ኬላ/ ፣ ማን እንደከለከለና በማን ትዕዛዝ እንደተከለከለ ለይተው በጽሑፍ ለቤቱ እንዲያቀርቡ ማሳሰቢያ ተሰጥቷቸዋል ፡፡

አያይዘውም አንቀጽ 29ን በተመለከተ እስከ አሁን ድረስ ከተሰነዘሩት አስተያየቶች መካከል ንዑስ አንቀጽ 5 ብሔር/ ብሔረሰቦችና ሕዝቦችን ለማስተናገድ በሚያስችል መልኩ እንዲስተካከል ፣ ንዑስ አንቀጽ 3 ደግሞ የማስራጨት መብት እንዲጨመር በሚያስችል መልኩ እንዲስተካከል ፣ ንዑስ አንቀጽ 6 እንዳለ እንዲሰረዝ የሚሉ የተቃውሞ ሀሳቦች መቅረባቸውን ጠቁመው ከእነዚህ በተጨማሪ የሚቀርቡ የተቃውሞ ሀሳቦች ካሉ ሊቀርቡ እንደሚችሉ ገልጸዋል ፡፡

በዚህም መሠረት አቶ ዘለሌ ፀጋሥላሴ ከክልል 14 በንዑስ አንቀጽ 1 ማንኛውም ሰው የመሰለውን አመለካከት መያዝ እንደሚችል መገለጹ ፣ የፕሬስ ነጻነትም በሌሎች ንዑሳን አንቀጾች መቀመጡንና የፕሬስ ነፃነት ሲባል ግን የመሰለውን ነገር መናገር መጻፍ እንዲሁም ማስተላለፍ በመሆኑ ይህ በሚደረግበት ጊዜ የአንድን ሰው የፕሬስ ውጤት ከሌላ ሰው አመለካከት ጋር ሊፃረር እንደሚችል ፣ የዚህ ዓይነት ሁኔታ ሲያጋጥም ለሕዝብ ከሚሰጠው ዲሞክራሲያዊ መብት አኳያ የፕሬስ ውጤትን ለሕዝብ ግምገማ ትቶ ሕዝቡ የመሰለውን ፍርድ እንዲሰጥ ማድረግ እንጂ ገደብ ማድረግ እንደማይገባው ፣ በዚህ ረገድም በንዑስ አንቀጽ 6 የተቀመጠው ገደብ ጠንካራና የማይገባ በመሆኑና የሕጎች ሁሉ የበላይ በሆነው ሕገ መንግሥት ውስጥም በአንድ በኩል የፕሬስ ነፃነትን ማረጋገጥ በሌላ



በኩል ደግሞ ገደብ ማስቀመጥ ሊረጋገጥ ከሚፈለገው ዲሞክራሲያዊ መብት ጋር የሚፃረር በመሆኑ 1-5 ያሉትን ንዑሳን አንቀጾች እንዳሉ ተቀምጠው ንዑስ አንቀጽ 6 ግን መሰረዝ አለበት የሚል ሀሳብ አቅርበዋል ፡፡

ከዚያም ተጨማሪ የተቃውሞ ሀሳብ ባለመኖሩ የድጋፍ ሀሳቦች ሊቀርቡ እንደሚችሉ የጉባኤው ሊቀመንበር በገለጹት መሠረት አቶ አብዱልቃድር ሙሐሊም ከክልል 5 የኮሚቴውን ሀሳብ እንደሚደግፉ ገልጸው በተለይ በንዑስ አንቀጽ 5 የመንግሥት ፕሬሶች የተለያዩ አስተያየቶችን እንዲያስተናግዱ መደረጉ የተገባ መሆኑን ፣ ጠቅላላ አንቀጹም አስፈላጊ በመሆኑ እንዳለ ቤቱ አፅድቆት ግለሰቦች ሆኑ የክልል መስተዳድሮች የዚህ መብት ተጠቃሚ መሆን እንደሚኖርባቸው ገልጸዋል ፡፡

በማስከተልም አንድ የክልል 2 ተወካይ ደግሞ ሀሰት የሆነ ነገር ለዚህ ታላቅ ጉባኤ መናገር አሳፋሪ እንደሆነ ፣ በዚህ ረገድ የግል ጋዜጦች ኬላ ላይ ይታገዳሉ የተባለው ሲደረግ ያልታየ ሀሰት እንደሆነና ይህን የተናገሩት ግለሰብ ከዚህ ቀደምም ተመሳሳይ የተሳሳተ መረጃ የሌለው ኢንፎርሜሽን ያቀረቡ በመሆኑ ይህ ሁኔታ ገደብ ሊበጅለት እንደሚገባ ገልጸው ከኮሚቴው ማሻሻያ ሀሳብ ጋር አንቀጽ 29 እንዳለ እንዲፀድቅ ቢደረግ እንደሚጠቅም አመልክተዋል ፡፡

ቀጥሎም አቶ አባይ ፀሐዬ ከክልል 1 በአንቀጽ 29 ላይ የተቀመጡትን የአመለካከትና ሀሳብን በነፃ የመያዝና የመግለጽ ነፃነቶችን በተመለከተ የቀረቡ የተቃውሞ ሀሳቦች የተጣመሙና ዲሞክራሲን አደጋ ላይ የሚጥሉ እንደሆነ ጠቁመው ከ1-6 ባሉት ንዑሳን አንቀጾች የተዘረዘሩት መብቶች በማንም ዲሞክራሲያዊ አገር ሕገ መንግሥት ውስጥ ሊካተቱ የሚገባቸውን ነጥቦች ያካተቱ እንደሆነ ሲገልጹም ፣

- ማንኛውም ሰው ትክክል ነው የሚለውንና የመሰለውን አመለካከት መያዝ እንደሚችል በንዑስ አንቀጽ 1 እንደተቀመጠ ፣
- በንዑስ አንቀጽ 2 ደግሞ የመሰለውን አመለካከት መያዝ ብቻ ሳይሆን አመለካከቱን ለመግለጽ ወሰን ሳይደረግበት ፣ በኬላ ሳይታገድ ፣ በማንኛውም የማስራጫ ዘዴ ማስራጨት እንደሚችልና ይህም አመለካከቱና ሀሳቡ እንዴት እንደሚገልጽና እስከ ምን ድረስ መግለጽ እንደሚችል በዝርዝር የተቀመጠ መሆኑን ፣
- በንዑስ አንቀጽ 3 የተቀመጠው ደግሞ በሀገራችን ከዚህ ቀደም በፍፁም ያልነበረ የቅድመ ምርመራ /ሳንሱር / ሥርዓት አለመኖር የተረጋገጠበት ፣ ቅድመ ምርመራ እንዳስፈላጊነቱ የሚኖር ሳይሆን በማንኛውም መልኩ

የተከለከለ መሆኑን ፣ ማንኛውም ሰው ኃላፊነቱን ሁሉ ራሱ ወስዶ ሀሳቡን የሚጽፍና የሚያትምበት፣ የሚያሰራጭበት ሁኔታ በግልጽ የተቀመጠ መሆኑን አብራርተዋል ::

እስከተለውም ከላይ የተዘረዘሩት የፕሬስ ነፃነት ምሰሶዎች አመለካከትን የመያዝ፣ የማሰራጨትና መረጃ የማግኘት ነጻነቶች ሙሉ በሙሉ ከተረጋገጡ በኋላ በንዑስ አንቀጽ 4 ደግሞ ለፕሬስ የሕግ ጥበቃ እንደሚደረግለት መንግሥትን ኃላፊነትና ግዴታ ውስጥ የሚያስገባ ሀሳብ እንደተቀመጠ ጠቅሰዋል ::

በዚህ ሁኔታ ንዑስ አንቀጽ 6 የተወሰኑ ገደቦች መቀመጣቸውንና እነዚህ ገደቦች ፍፁም መኖር የለባቸውምና ንዑስ አንቀጹ ይውጣ ብሎ በደፈናው ከመናገር በቅድሚያ የንዑስ አንቀጹን ትርጉም ምን እንደሆነ ፣ ተሻሽሎ በቀረበበት ሁኔታ ቢቀመጥ ሕዝብን መጉዳት አለመጉዳቱ ፣ ቢወጣ ዲሞክራሲን ማስፈን አለማስፈኑን ሊጤን እንደሚገባው አሳስበዋል ::

አያይዘውም ንዑስ አንቀጽ 6 ከዚህ ቀደም በኃይሌሥላሴና በደርግ ዘመን እንደተደረገው በደፈናው ሕግ በሚፈቅደው መሠረት መጻፍ ፣ መናገር ፣ ወዘተ... ይቻላል ተብሎ የተቀመጠና ወደፊትም በሕግ ሰበብ መብቶች መልሰው የሚታፈኑበት ሁኔታ ሳይሆን ሕጋዊ ገደብ የማይደረግባቸውና የሚደረግባቸው ነገሮች በራሱ በሕገ መንግሥቱ ተለይተው እንደተቀመጡ ጠቅሰው ከ1-5 ያሉት ንዑሳን አንቀጾች የተዘረዘሩትን መብቶች ተጠቅሞ የሚቀረበው የፕሬስ ውጤት በአስተሳሰባዊ ይዘትና ሊያስከትል በሚችለው አስተሳሰባዊ ውጤት ምክንያት ገደብ ሊደረግበት እንደሚችልና በሐቅ ላይ የተመሠረተና ሰላማዊና ሕጋዊ መንገድ እስከ ተከተለ ድረስ የፈለገውን ያህል ውጤት ቢያመጣ ፣ የፈለገውን ያህል የአቋም ለውጥ ቢያስከትል ፣ ለምሳሌ ሕዝቡን በጠቅላላ ያለው መንግሥት እንደማይጠቅም ሊያሳምን ቢችል ፣ ገደብ ሊደረግበት እንደማይችል በንዑስ አንቀጽ 6 መቀመጡን አብራርተዋል ::

አክለውም ገደብ እንዲደረግ ያስፈለገው ግን የሕፃናትንና የወጣቶችን ሥነ ምግባርና ሞራል የሚጎዳ ፣ ባሁኑ ሰዓት አውሮፓውያን ሳይቀሩ ለመግታት ያስቸገራቸውን ዓይነት የሥነ ምግባር መበላሸት የሚያስከትል ከሆነ ፣ የሰው ክብርንና መልካም ስምን የሚያጠፋ ከሆነ ፣ የጦርነት ቅስቀሳዎችን የሚያስተጋቡና ሰብአዊ ክብርን የሚያጎድፉ የአደባባይ መግለጫዎች የወጡ እንደሆነ ፣ እዚህ የመላውን ኅብረተሰብ ሞራልና ክብር የሚያዋርዱ ፣ ሰላምን የሚያጠፉ የፕሬስ



ውጤቶችን በሕዝቡ መካከል እየረጩ ልኑር ማለት ደግሞ ዲሞክራሲ እንዳልሆነና በተጠቀሱት ጉዳዮች ላይ ገደብ የማያደርግ ማንም ዲሞክራሲያዊ አገር እንደሌለ ገልጸዋል ::

አያይዘውም የኅብረተሰቡን ክብርና ሞራል በሚያዋርዱ የፕሬስ ውጤቶች ላይ ሕጋዊ ገደብ እንዲደረግ የሚደነግገው ንዑስ አንቀጽ 6 እንዲሰረዝ ሀሳብ ከማቅረብ በቀጥታ የወጣቱን ሥነ ምግባር ይበላሽ ፣ የኅብረተሰቡ ክብርና ሞራል ይጉደፍ ብሎ በግልጽ መናገር እንደሚቀል ገልጸው የዚህ ዓይነቱ አስተሳሰብ አዲስ ሳይሆን ሕዝብን እንደ ሕዝብ የሚያዋርድ ፣ የሚያጋጭና ሃይማኖትን የሚያንቋሽሽ ነገር እየጻፉ ሕዝብ አይጠይቀንም ከሚል የመነጨ ፣ የግል ጋዜጦች በየክልሉ ሄደው ተዘዋውረው መሸጥ ሲያቅታቸው ከአዲስ አበባ እንዳንወጣ ኬላ ላይ ታግደናል ከሚለው ሰበብ ጋር የተያያዘ ፣ ያሉት የግል መጽሔቶች ልቅነታቸውን እንደያዙ ያለ ሕጋዊ ገደብ እንዲቀጥሉ ለመስበክ ከሚደረግ ጥረት የመጣ እንደሆነ አመልክተዋል ::

ከላይ የተጠቀሱት ሥነ ምግባርን የሚያጎድፉ ጽሑፎችና የፕሬስ ውጤቶች ሕጋዊ ገደብ ይደረግባቸዋል ቢባልም ሳንሱር ይደረጋሉ ሳይሆን ከታተሙና ከተሰራጩ በኋላ አቃቤ ሕግ አይቶ በርግጥ የኅብረተሰቡን ሞራል የሚያበላሹና ሰላምን የሚያደፈርሱ ከሆኑ በሕግ እንደሚጠይቃቸው እንደተደነገገ ፣ ይህ ከተሰራጨ በኋላ መጠየቅ ጉዳት ቢኖረውም እንኳን በሳንሱር ሰበብ ቀናና ለሕዝብ የሚጠቅሙ ሀሳቦችም አብረው እንዳይጻፉ የተወሰነውን ተሸክሞ በአገሪቱ ዲሞክራሲ ስፋት እንዲኖረው ለማድረግ እንደተሞከረ ፣ በመሆኑም አንቀጽ 29 ከኮሚቴው ማሻሻያ ጋር ተቀባይነት ሊኖረው እንደሚገባ አሳስበዋል ::

ከዚያም አቶ ሀሰን አሊ ከክልል 4 የአቶ አባይ ፀሐዬ የመከራከሪያ ነጥብ እንደተቀበሉት ገልጸው አንቀጽ 29 ንዑስ አንቀጽ 3/ለ/ ን በተመለከተ ግን መስተካከል የሚኖርበት ጉዳይ እንዳለ ጠቀመው በንዑስ አንቀጽ 3/ለ/ ጋዜጠኞች የሕዝብን ጥቅም የሚመለከት መረጃ የማግኘት ዕድል እንጂ መብት እንዳላቸው እንዳልተቀመጠ ፣ የሀገርን ሚጥስር የሚመለከት የሕዝብን ጥቅም ሊጎዳይ የሚችልን የመንግሥት ሚስጥሮችን ሁሉ ማንኛውም ጋዜጠኛ በፈለገ ጊዜ የማግኘት መብት የሌለው መሆኑን ሊታወቅ እንደሚገባና በማንኛው ዲሞክራሲያዊ አገሮች የተለመደው አሠራር መንግሥት ለጋዜጠኞች ኢንፎርሜሽን የሚሰጠው የኅብረተሰቡን ጥቅም እንደማይጎዳ ካረጋገጠ በኋላ እንደሆነ ፣ ለምሳሌ የፔንታጎንን ሚስጥር የታይምስ ወይም የኒውስ ዊክ መጽሔቶችና ጋዜጦች አገኛለሁ የማለት መብት እንደሌላቸው ገልጸው በተጨማሪም ጋዜጠኞች ኢንፎርሜሽን የማግኘት ዕድል አላቸው ሲባል ማንኛውንም ባለሥልጣን በማንኛውም ጊዜ አስገድደው ኢንፎርሜሽን እንዲሰጣቸው ያደርጉታል ማለት እንዳልሆነና የመንግሥት

ባለሥልጣኑም መብቱ ተከብሮለት ኢንፎርሜሽን ሲጠየቅ የመተባበር ኃላፊነት እንዳለበት መገንዘብ እንደሚገባ አስረድተዋል ፡፡

ከዚያም የጉባኤው ሊቀመንበር ዶ/ር ነጋሶ ጊዳዳ እንደ ብሔር / ብሔረሰቦችና የሃይማኖት መብቶች ሁሉ የመገናኛ ብዙሃን ጉዳይ ሲነሳም ኩዮቁን ብሔር/ ብሔረሰቦች በኩል የሚነሱ ፍራቻዎች እንዳሉ ፣ ከደቡብ ኢትዮጵያ ሕዝቦች ክልል የአቶ አለሙ ፎቼ ሥጋትም ከዚህ ዓይነት ፍራቻ የመጣ እንደሆነ ገልጸዋል ፡፡

አያይዘውም በኢትዮጵያ በአሁኑ ወቅት 229 ጋዜጦችና መጽሔቶች ፈቃድ የወሰዱ ሲሆን በገንዘብና ተቋማቸውን የማሟላት ችግር ምክንያት ፈቃድ ሳያገኙ ከቀሩት ውጭ በስተቀር 60ዎቹ በመንቀሳቀስ ላይ እንደሚገኙ ፣ በመንግሥት የሚካሄድ ወይም በመንግሥት ቁጥጥር ሥር ያለ መገናኛ ብዙሃን የሚለውን አገላለጽም ለጊዜው እንጂ ለወደፊቱ ወደ ሕዝብ መገናኛ ብዙሃንነት የሚቀየሩበት ሁኔታ እንደሚመቻችና እንደተቃረበም ፣ በተጨማሪም መገናኛ ብዙሃን የማዕከላዊ መንግሥት ብቻ ሳይሆን የክልል መስተዳድሮችም የራሳቸውን ማቋቋም እንደሚችሉ በክልል መስተዳድሮች አመሠራረት አዋጅ እንደተደነገገና ለወደፊቱም ይህ እንደሚጠናከር ፣ የተለያዩ ብሔር / ብሔረሰቦችም ፍላጎትና ችሎታ ካላቸው የራሳቸውን የመገናኛ ብዙሃን ለማቋቋም እንደሚችሉ ገልጸው የማዕከላዊ መንግሥት መገናኛ ብዙሃን የተለያዩ ብሔር / ብሔረሰቦችን ባህሎች የማስተናገድ ፣ በልዩ ልዩ ብሔር /ብሔረሰቦች ቋንቋዎች የማስተላለፍ ፍጎት ብቻ ሳይሆን ግዴታም እንዳለባቸውና ይህንንም ቀስ በቀስ ተግባር ላይ በማዋል ላይ እንደሚገኙ ጠቅሰው በአንቀጽ 29 ንዑስ አንቀጽ 5 የተለያዩ አስተያየቶችን ለማስተናገድ መቻል እንዳለባቸው ሲገልጽ አጠቃላይ የፕሬስ ነፃነትን የሚያመለክት በመሆኑና የብሔር/ ብሔረሰቦችንና የሕዝቦችን መብቶች በሚመለከተው አንቀጽ ሲደረስ መወያየት ስለሚቻል በንዑስ አንቀጽ 5 የተለያዩ አስተያየቶችን ፣ ብሔር / ብሔረሰቦችንና ሕዝቦችን ለማስተናገድ የሚል እንዲጨመር የሚለው የውሳኔ ሀሳብ የግድ ካልሆነ በቀር ለውሳኔ ባይቀርብ እንደሚሻል አሳስበው በአንቀጽ 29 ላይም በአጠቃላይ እና በንዑስ አንቀጽ 6 በተለይ ውሳኔ ተሰጥቶ እንዲታለፍ አሳስበዋል ፡፡

ከዚያም አንድ የጉባኤ አባል በአለፈው በአንድ ጋዜጣ ላይ የጋምቤላ ምክር ቤት ፕሬዚዳንቱንና ምክትል ፕሬዚዳንቱን ከሥልጣን አባርሮ እንደተበተነ መጻፉን፣ ከማዕከላዊ መንግሥት ሳይቀር ለክልል ምክር ቤቱ ስልክ ተደውሎ እንዲጠየቅ የተደረገበት ሁኔታ እንደነበር ፣ ሆኖም እንደ ክልል ምክር ቤት አባልነታቸው የተባረሩ ፕሬዚዳንትም ሆኑ ምክትል ፕሬዳንቱ አለመኖራቸውንና የተባረሩ ቢኖሩም በጥፋታቸው ሌሎች መሆናቸውን እንደሚያውቁ ፣ እንደዚሁም ጥቁር አንበሳ የመንግሥቱ ኃይለማርያም ጦር ጋምቤላ ገብቶ ሕዝቡ እንደተቀበለው በጋዜጣ



እንደተጻፈ ፣ ይህ ግን ሀሰትና የክልልን መብት የደፈረ የሕዝቡን ሞራል ያንቋሸሸ እንደሆነ ኢንፎርሜሽን አቅርበዋል ፡፡

የጉባኤው ሊመንበር ዶ/ር ነጋሶ ጊዳዳ የቀረበው ዓይነት ኢንፎርሜሽን በርካታ መሆናቸውን ጠቁመው በአንቀጽ 29 ላይ ውሳኔ እንዲሰጥበት አሳስበዋል ፡፡

በዚህም መሠረት ፣

አንቀጽ 29 ንዑስ አንቀጽ 6 "እነዚህ ገደብ ሊጣልባቸው የሚችለው የሀሳብና መረጃ የማግኘት ነፃነት በአስተሳሰባዊ ይዘቱ እና ሊያስከትል በሚችለው አስተሳሰባዊ ውጤት ሊገታ አይገባውም በሚል መርህ ላይ ተመስርተው የወጡ ሕጎች ብቻ ይሆናሉ ፡፡ የወጣቶችን ደህንነት ፣ የሰውን ክብርና መልካም ስም ለመጠበቅ ሲባል ሕጋዊ ገደቦች በእነዚህ መብቶች ላይ ሊደረጉ ይችላሉ ፡፡ የጦርነት ቅስቀሳዎች እንዲሁም ሰብአዊ ክብርን የሚነኩ የአደባባይ መግለጫዎች በሕግ የሚከለከሉ ይሆናሉ ፡፡ ስለሆነም ማንኛውም ዜጋ ከላይ በተጠቀሱት መብቶች አጠቃቀም የሚጥሱ ሕጋዊ ገደቦችን ጥሶ ከተገኘ በሕግ ተጠያቂ ሊሆን ይችላል ፡፡ "

የሚል መሆኑን የጉባኤው ዋና ጸሐፊ ከተነበበ በኋላ በረቂት ሕገ መንግሥቱ ንዑስ አንቀጽ 6 ምትክ ገብቶ እንዲፀድቅ ለድምፅ ቀርቦ ድጋፍ 505 ፣ ተቃውሞ 3 ተመዝግቦ ያለምንም ድምፀ ተአቅቦ ፀድቋል ፡፡

ቀጥሎም አንቀጽ 29 ከነሻሻያው እንዲጠድቅ ለድምፅ ቀርቦ ድጋፍ 505 ፣ ተቃውሞ 3 ተመዝግቦ ያለምንም ድምፀ ተአቅቦ ተቀባይነት አግኝቶ ፀድቋል ፡፡

በጨረሻም ስብሰባው ከሰዓት በኋላ የብሔር / ብሔረሰቦች መብት ኮሚቴ ስብሰባውን በጉባኤው አዳራሽ እንደሚያደርግና በቦታው የተወካዮች ምክር ቤት ፀሐፊ አቶ ተስፋዬ ሀቢሶ ተገኝተው የብሔር/ ብሔረሰቦች የራስን ዕድል በራስ የመወሰን እስከ መገንጠል የሚለውን ማካተት የለበትም የሚል ሀሳብ ይዘው ንግግር ስለሚያደርጉ የሚፈልግ ጉባኤተኛ መገኘት እንደሚችል አሳስበው የዕለቱ ስብሰባ ከቀኑ 7:20 ሰዓት ተጠናቋል ፡፡